# የጉራጌ ህዝብ የፖለቲካ ትግል

# እና

# የሃገራዊ ብሔራዊ ምክክሩ

**(ክፍል - 1)**

**ለጉራጌ ምሁራንና ፖለቲከኞች (ልሂቃን) ምክክር**

**የተዘጋጀ ፅሁፍ**

**በፍቅርአለም ከበደ**

**()**

**አዲስ አበባ ፤ ኢትዮጵያ**

**ጥር 2014 ዓ/ም**

## I. ማዉጫ

*ማውጫ .........................................................................................2*

*መግቢያ ........................................................................................3*

1. *የሰነዱ አስፈላጊነት.....................................................................4*
2. *ጥንታዊ ጉራጌ ሕዝብ አስተዳደር ..............................................................5*
3. *የዘመናት የጉራጌ ህዝብ የፖለቲካ ተሳትፎ፤ ጥያቄዎችና ችግሮች ዳሰሳ....................6*
4. *የጉራጌ የፖለቲካ አስተላለፍ ብያኔ፤ የፖለቲካ ትግልና ብሔርተኝነት ..............................10*
5. *ወቅታዊ የጉራጌ ፖለቲካ ተዋናዮች የአስተላለፍ ሁኔታ....................................18*
6. *ለውጡ፤ ሀገራዊ አሁናዊ የፖለቲካ ሁኔታዉና ብሔራዊ ምክክሩ .........................22*
7. *ቀጣይ የጉራጌ ህዝብ ትግል አቅጣጫና ብሄራዊ ምክክሩ......................................25*
8. *አዲሱ ኢትዮጵያዊነት ከጉራጌነት ይወለድ.....................................................28*
9. *መደምደሚያ..........................................................................................32*

## II. ***መግቢያ***

በመፃኢ የኢትዮጵያ ፖለቲካ ውስጥ እንደሀገር በተለይመም እየተንደረደርንበት ካለነው የዘመናት የፖለቲካ ቁርሾዎች፣ ጥያቄዎች እና የተራራቁ ፍላጎቶችን በሀገር ልጅነት፤ በኢትዮጵያ ጥላ ስር ተሰባስቦ የመመካከር አስፈላጊነትና ዘላቂ ሃገራዊ መፍትሔ ያልተገደበ፣ አካታች፣ ሁሉ አቀፍ ብሔራዊ ምክክር መድረኮች እየተሰናዱ ይገኛል። ይህ ፅሁፍ ዝግጅትም ጉራጌ ህዝብ የጉራጌ ህዝብ ታሪክ ፣ ባህልና እሴቶች እንዲሁም ፍልስፍናዎችና መሰረቶቻቸው በመነሳት፤ የጉራጌ የአመታት የፖለቲካ ትግል አነሣስና ማደግ፤ ወቅታዊ ሁኔታና ብሄርተኝነቱ በዝርዝር በመዳሰስ፤ የህዝባዊ ትግሉ ቀጣይ መዳረሻ በማመላከት፤ በኢትዮጵያ ፖለቲካ ዉስጥ ጉራጌው የሚጠበቅበትን ሚና እንዴት ሊጫወት እንደሚገባ እና የመሳሰሉ በሳል የፖለተካ ጥያቄዎችን መሰረት አድርጎ ለማቅረብ ተሞክሯል።

## 1) የሰነዱ አስፈላጊነት

የጉራጌ ፖለቲካ ባብዛኛዉ proactive ከመሆን ይልቅ reactive እና ችግሮች የበለጠ ጉዳት እንዳያደርሱ ማዳፈን ላይ የተመሰረተ እየሆነ እየሄደ ቀጥሏል። አሁን የሚታየው ነገር ወረቀት ላይ የሰፈረ ስትራቴጅ በተለይም ምን ሊፈጠር ይችላል ከተፈጠረስ የምንወስደዉ ግብረ መልስ ምንድን ነዉ፤ እንዳይፈጠርስ ምን እናድርግ የሚል (scenario build በማድረግ) ስትራቴጅ አስቀምጠን ወደፊት መራመድ እየቻልን አይደለም። የኢትዮጵያ የፖለቲካ ጉዞ እንዲህ አይገመቴ እና ተለዋዋጭ መሆኑም መረዳት እና በሁኔታዎቹ ባለመገደብና ባለመወሰን፤ የማህበረሰቡን በማታገል፤ መታደግና ብሎም ተገዳደሪ ሆኖ ጥቅሙን ከማስከበር የተሻለ አማራጭ የለም።

ያሉንን አማራጮች በመመርመር በየጊዜዉ ህዝባችን ላይ የሚደርሰዉን የህልውና አደጋ እና ጉዳት በሰፊዉ መቀነስ ብሎም ማስቀረት ይቻላል። ልሂቃኖች ሰብሰብ ብለዉ ፖለቲካዊ፤ ኢኮኖሚያዊ፤ ማህበራዊ እና የጸጥታ ጉዳዮችን በሚገባ በማጥናት በተለይም ቀጣይ አመታቶች ሊከሰቱ የሚችሉ ፖለቲካዊ እና ኢኮኖሚያዊ ቀዉሶችን ሳይንሳዊ ጥናት በማካሄድ የመፍትሄ ሃሳቦች እና ስትራቴጅዎች በዶክመንት መልክ መዘጋጀት ይጠበቅባቸዋል። በጉራጌ ህዝብ ያሉትን የፖለቲካ አማራጮች በተገቢው እንዲረዳ፣ እንዲመረምር እና እንዲወስን ማድረግ እና እንዲታገል ማድረግ ካልተቻለ ሕብረተሰቡንም ቀላል ያልሆነ ዋጋ እየከፈለ ይቀጥላል።

ሌላው ሀገር ቤት በዞኑ ካለው ህዝብ ባሻገር በለያዩ የተለያዩ አካባቢዎች ያለዉ ጉራጌ በምን መልኩ ከአደጋ ተጋላጭነት ሊወጣ ይችላል የሚለዉ ትልቁ እና እስካሁንም ስትራቴጅ ያላወጣንለት ጉዳይ ነዉ። ይሄን ማህበረሰብ አቅሙን የማሳደጊያ ስልቶች፤ በትውልድ ቀየው በሚደረግ የፓለቲካ እንቅስቃሴዎች በቅርበት በመከታተል ከሐገሪቱ የፓለቲካና የኢኮኖሚ ጉዞ ጋር እንዲስተካከል ለማድረግ፤ እራሱን ባለበት ቦታ የሚከላከልበት ኔትወርክ የመዘርጋት ስራወች፤ እንዲሁም ተጋላጭነቱን ሊቀንሱ የሚችሉ የኢኮኖሚ እና የፖለቲካዊ ጥንካሬ ልንፈጥርለት ይገባል። ይሄም ማህበረሰባችን ከአኗኗር ዘይቤዉ፤ ከተሰማራበት ስራው፤ በሚኖርበት አካባቢ ካለዉ ከሌላዉ ማህበረሰብ ጋር ያለዉ የግንኙነት አይነት እና መሰል ጉዳዮች ተጠንተዉ ማህበረሰባችን የተሻለ የፖለቲካ እና ኢኮኖሚ አቅም እንዲሁም መብቱ እንዲከበርለት አማራጭ እንዲከተል የማድረግ ሰፊ ስራ ያስፈልጋል። ግን እያደረግነው አይደለም።

አሁን የምናያቸዉ ክስተቶች ወደፊትም በቀላሉ የሚቆሙ አለመሆኑን በብዙ መልኩ መገንዘብ ይቻላል፡፡ ዋጋ መከፈሉም ይቀጥላል፡፡ ህዝቡ በለውጡ መንግስት ያለዉ አተያይ (real/perceived weakness) እና መሪዎቹ ደጋፊ ለመገንባት የሚከተሏቸዉ ግልፅ ያልሆኑ አቋሞቻቸው ለመቃወምም ሆነ ለመደገፍ የማይቻል ቅርፅ () አልባ መሆናቸው፤ ህብረተሰቡ መብቱን የመጠየቅና ህግን የማስከበር ዝንባሌዉ እየወረደ የመጣ በመሆኑ፤ የቆየዉ የማህበረሰቡ እሴት እና ሞራል የተሸረሸረ መሆኑ፤ እንዲሑም አሁን በእኛው በአክቲቪስቶች፣ በፖለቲከኞች ጭምር በእለት ተእለት የምንሰማቸዉን ወጥነት የሌላቸው እና ዝብርቅርቅ አስተላለፎች፤ ጥርት ያሉ ሃሳብና ስትራቴጂ ያለመኖር እንዳለሆኖ ሌሎች የፖልቲካውን ሃዲድ ለዘመናት ተከትለው ለድርድርና ለማሸነፍ ሲሰናዱና ሲዘጋጁ የጉራጌ ልሂቃን ገና ተራርቀው የቆሙ እና እንኳን ህዝብ እራሳቸውን የማያድኑ መሆናቸው፤ የትግሉ ስብራቶች ሆነው ቀጥለዋል፡፡ ግልፅ ስትራቴጂ አዘጋጅተን እየተጓዝን ባለመሆኑ የእኛ የፖለቲካ እንቅስቃሴ ሌሎች በሚያደርጉት የፖለቲካ እንቅስቃሴ ለይ ተመስርቶ reactive እንደሆነ መቀጠሉ ለሁሉም የጉራጌ elite ህመም ነው፡፡

ይህንን ሁኔታ ለመቀየር በጉራጌ ስም የሚንቀሳቀሱ ሁሉም ወገኖች ከልዩነታቸው ባሻገር ቢያንስ አደጋ ላይ የወደቀውን የጉራጌ ህዝብን ህልውና ለማስቀጠል እና እንደሰው ሊከበሩለት የሚገቡትን ሰብአዊ መብቶቹን ለማስከበር በሚያስችሉ ጉዳዮች ላይ የሚይዙት የጋራ አቋም ሊኖራቸው ያስፈልጋል፡፡ ይህ ሰነድ ያስፈለገውም የጉራጌ ህዝብን ህልውና ለማስከበር በጉራጌ ስም የሚንቀሳቀሱ ሁሉም ኃይሎች መካከል በቀጣይ የፖለቲካ ምእራፍ እና እንዲሁም ለዘለቄታውም ሊኖር የሚገባው የጋራ አቋምና አስተላለፍ ላይ ነጥቦችን ለመጠቆም ነው፡፡ በሃገራችን በቅርቡ ሁሉንም የፖለቲካ ኃይሎች የሚሳትፍ ሀገራዊ ምክክር እንደሚደረግ መንግስት ይፋ መሆኑና አስፈላጊው ቅድመ ዝግጅት እየተደረገ መሆኑ ደግሞ የዚህን ሰነድ አስፈላጊነት አስቸኳይ ያደርገዋል፡፡

## 2) የጉራጌ ሕዝብ ጥንታዊ የአስተዳደር

የጉራጌ ህዝብ ሰፍሮበት የነበረው መልከዓ ምድር እና ህዝቡም የነባሩ የኩሻዊ ቋንቋ ተናጋሪ (ያፈር ሰብ) እና የሴማዊያኑ (በተለያዩ ዘመናት ወደ አካባቢው የመጡ ህዝቦች) የቋንቋና ባህል ውርርስ ተዛምዶ ውጤት ነው፡፡ በታሪክ የጉራጌ ህዝብ የሰፈረበት ምድር በሰሜን ምስራቅ እና በሰሜን አዲስ አበባ፣ በደቡብ ምዕራብ የጊቤ ወንዝ፣ በደቡብ ከሃድያ እንዲሁም በሰሜን ምስራቅ ከዝዋይ ሀይቅ ጋር የሚዋሰን ነበረ፡፡ ለዚህ ሰይፈ ድባቤ፤ አዝማች፤ የጉራጌ ህዝብ አጭር ታሪክ፤ (1966 ዓ/ም) ጨምሮ ብዙ አብነቶችን መጥቀስ ይቻላል፡፡ አሁንም ይህ መልከዓ ምድር ከጉራጌ በተጨማሪ የኦሮሞ፣ የስልጤ፣ የማረቆ እና የቀቤና የተዛምዶ (ውህድ) ማንነትን

ይዘው ያሉ ህዝቦች አካባቢን የሚሸፍን አሰባሳቢ የጋር ማንነት የገነቡ ህዝቦች መገኛ ነው። በጥንታዊት ኢትዮጵያ፣ በመካከለኛዋ ኢትዮጵየም ሆነ በዘመናዊት ኢትዮጵያ ውስጥ የአገራችን ሕዝቦች የራሳቸው በሆነ ጥንታዊ የአስተዳደር ስርዓት ሲተዳደሩ የነበረ ሲሆን የአደረጃጀት ስርዓቱ በዋናነት ያልተማከለ የግዛት አስተዳደር ስርዓትን ይከተሉ ነበር።

ስለጉራጌ ታሪክ የጥንቱን ለምርምርና ጥናት ትተን በመካከለኛው ዘመን የአይመለል መንግስት ‹‹እንጀሪ›› ሸንጎ አስተዳደር እስከ አሁን በጉራጌ ጥንታዊ ባህላዊ አስተዳደሮች ሙሉ በሙሉ ተመሳሰይ ስርዓት በውስጣቸው የያዙ ናቸው። ለዚህ ንጋቱ ወልዴ፣ አፈንዲ ሙተኪ፣ አለቃ ተክሌ፣ ታምራየው ሲማ፣ ድንበሩ አለሙና ጓደኞቹ የመሳሰሉ በርካታ ፀሀፍያንን ስራዎችን በእማኛነት መጥቀስ እንችላለን። የጉራጌው ህዝብ እድገትና መስፋፋትን ተከትሎ እነዚህም ባህላዊ አስተዳደሮች እንደበዙ ይታመናል። ፕሮፌሰር በሃሩ ዘውዴ ‹‹Society, State & History; Selected Essays, 2008›› አዳስ አበባ ዩንቨርስቲ ፕሬስ ባሳተመው ስብስብ ስራቸው ውስጥ ‹‹የጆካቂጫ›› የሰባት ቤተ-ጉራጌን (ቸሃ፣ ጉመር፣ እነሞርና ኤነር፣ ምሁርና አክሊል፣ እዣ፣ ጌቶ እና እንደጋኝ)፤ ‹‹የጎርደና ሴራ›› (የስልጤ፣ የሶዶ እና የገ/ጉ/ወ)፤ ‹‹ፈራገዘኘ›› የመስቃን፤ ‹‹ሲናኖሴራ›› የዶቢ፤ ባህላዊ አስተዳደሮች ሲሆኑ የጎሳዎችን ውክልና መሰረት ባደረገ መልኩ መሪዎች የሚሰየሙባቸው ሲሆኑ ሁሉም ባህላዊ አስተዳደሮች ሕዝቡ ራሱን በራሱ የማስተዳደር እድልን የዘረጉ ያልተማከሉ ተመሳሳይ የአመራር፣ የፍትህ የአስተዳደር ስርዓት ያላቸው መሆናቸውን ጽፈዋል። እነዚህ የግዛት አካባቢዎች የተማከለ መንግስት ባይኖራቸውም ራሳቸውን ከባዕዳን ጥቃት የሚከላከሉበት፣ የውስጥ ሰላማቸውን የሚያረጋግጡበት፣ ተጠያቂነትን የሚያሰፍኑበት እንዲሁም የወል እሴቶችን በተገቢ ሁኔታ የሚገለገሉበት ጥንታዊ አደረጃጀትና ሥርዓት ነበሯቸዉ። በርካታ ምሁራን በፅሁፎቻቸው በጉራጌ ምድር ዘመናዊው ዓለም ህግ ጋር የሚስተካከል የአስተዳደር ስርአት የነበረ መሆኑን በመግለጽ ከትበዋል።

እነ ድምበሩ ዓለሙ ባዘጋጁና በ1987 ዓ.ም በታተመው ‹‹ጎጎት በጉራጌ ብሔረሰብ አጭር የታሪክ›› መጽሐፍ ላይ የጉራጌ ህዝብ ታሪክና ባህል ‹‹የጉራጌ ሕዝብ የተጋድሎ ታሪክ›› በሚለው ስድስተኛ ክፍል ውስጥ ብሔረሰቡ ከውጭ ወራሪዎች ጋር ብቻ ሳይሆን የውስጥ መቃቃር እንደነበርና በውይይት የመፍታት እረጅም ግዜ ባህልና ታሪክ የነበረን መሆኑን ያስረዳሉ። በተለይ በውስጥ የነበረው ችግር በወቅቱም እልባት ያገኘው ስላ ኦዳ በተባለ ጉራጌ ሰው ጥረት መሆኑ በገጽ 218 ተመልክቷል። በእሱ አነሳሽነት የስምምነት ጉባዔ ‹‹ጎጎት›› በተባለ ሥፍራ እንደተካሄደ፤ ጎጎት የሚባለው ስፍራ የሚገኘውም በዶቢና በሙህር ድንበር መሆኑ ተገልጿል። ሰላም ሰፍኖ እና ግጭቶች እንደዚ በመምክር እየተፈቱ ለሁለተኛና ለሦስተኛ ጊዜ ተመሳሳይ ጉባዔዎች በሌሎች

ሥፍራዎች መካሔዳቸውንም መፅሐፉ ይገልጿል። በተለይ አራተኛው ‹‹ታላቁ ጎጎት›› የተሰኘው ጉባዔ በ1928 ዓ.ም እነቆር ላይ እንደ ተካሄደው እና በጉርዳ (ቃልኪዳን) የተጠናቀቀ ነው (ገጽ 219)። አራተኛው ጉባኤ በኢትዮጵያ እና በአካባቢው ታሪክ ከፍ ያለ ዋጋ የሚሠጠው የሚያደርገው ታሪክም አለው ‹‹የአላባ፣ የቀቤና፣ የማረቆ፣ የስልጤ፣ የከምባታ፤ የሀዲያና የአማራ ተወካዮች›› በዚሁ ጉባዔ ተሳትፉበት መሆኑ ነው። አባቶቻችን እነኝህን ሕዝቦችን በጋራ አስተባብሮ የመምራት ቀደምት ታሪክ ፅፈዋል።በጉባዔ የተጠቀሱት ብሔረሰቦች በ1928 ዓ.ም ዳግም የመጣውን የጣልያን ወራሪ ጠላት በጋራ የመመከት ታላቅ ተጋድሎ ፈጽመዋል። የጣልያን ወረራ ለመመከት ደጃዝማች በቀለ ወያ እና ገረሱ ዱኪ የጦር መሪነት ጣልያንን አርበድብደዋል። ሁለቱ ጀነራሎ (ይልማ ሺበሺ እና ወልደስላሴ በረካ) ከዘመን ቀድመው ‹‹በራስ አገዝ›› ልማት ሃብት አሰባስበው እነኝህን ህዝቦች በመንገድ መሰረተ-ልማት በማስተሳሰር ቀጠናዊ ትስስር እዲፈጠር አድርገዋል። እነኚህ ቀደምት የስልጣኔ የአስተዳደር ስርአት እና ችግሮችን የመፍታት ነባር እሴት ከጉራጌነት የሚቀዱ ከኛ አልፎ ለሐገርም ይተርፋሉ የምንለው። ለዘመናት ሰው ሰርተዋል። አገር ገንብተዋል። ሀይማኖት አጽንተዋል።

## 3) የዘመናት የጉራጌ ህዝብ የፖለቲካ ትግል፤ ጥያቄዎች እና ችግሮች ዳሰሳ

ከጥንት ጀምሮ ነባሩ ጉራጌ የህዝብ አስተዳደር ፍልስፍና እና ስርአት በአካባቢውም እራስን በራስ የማስተዳደር እይታዎች ሆነ እንደ ሃገር ትልቅ ሆኖ ከብዙሃን ጋር በጋራ በመቆም አኪያ እጅግ ጥልቅ እሳቤዎች እና ከህይወት ልምድ የተወለደ በሀየማኖታዊ እና ባህላዊ እሴቶችን መንዝሮ ያጣመረና እንኳን ትናንትን ዛሬንና ነገን እንኳን የሰው ልጆች መሻቶችን የገመደ ነበር። ጉራጌነት ውህድ ማንነት ልቆ የተገነባው፤ የነባሩን ህዝብ (የአፈር ሰብ) እንድሁም በተለያዩ ግዜያት ወደ አካባቢው የተደረጉ በብዝሃነት ውስጥ የሚመነዘሩ የህዝብ አሰፋፈርና ማንነቶችን በብቃት ያስተናገደ ህዝብ ነው። ለዚነው ጉራጌነት አንዳንዶች አሳንሰው እንደሚያቀርቡት በፖለቲካ አስተዳደር የተፈጠረ ማንነት አይደለም የምንለው።

ከማንነቱ በሚቀዱ ጉራጌ ጠንካራ የስራ ባህል ያለው ታታሪ ህዝብ፣ የጎለበተ የተፈጥሮ ሃብት አጠቃቀም፣ የዳበረ የማህበራዊ ሀብት (Social-Capital) የገነባ፣ በዚህም ኑሮውን፣ አካባቢውብን እና ሀገሩን ያሻሻለ፣ በማያቋርጥ የህይወት ትግልና ለውጥ ውስጥ ያለ… ዘመናትን ያስቆጠረ ባህላዊ አስተዳደርና ህግ መስርቶ ዘመን የተሻገረ፣ በባህልና የሀይማኖት እሴቶቹ ሃገር ወዳድ፣ በስነምግባር የጎለበተ፣ ብዙ ተምሳሌታዊ ዜጎችን የፈጠረ እና በኢትዮጵያዊነቱ የማይደራደር ነው።

ጉራጌ ሀገሩን ከጣልያን ቅኝ ግዛት ለመታገል እንደ ሁሉም የኢትዮጰያ ብሔር ብሔረሰቦች በግዛት ማስከበር ያዳበረውን የውጊያ ልምድ ይዞ ለሀገሩ ደሙን አፍሷል፣ አጥንቱንም ከስክሷል፣ ጉራጌም ከወገኖቹ ጋር ዘምቶ የአገሩን ነፃነት አስጠብቆ ያኖረ ህዝብ ነው። በአንድነት በውስጥና በውጭ የተነሱ የሃገር ጠላቶች ላይ ክንዱን ያነሳ፣ በየዘርፉ ለሃገሩ የሚገባትን መስዋትነትን ሲከፍል የኖረ ህዝብ ነው። የጉራጌ ህዝብ ታሪክ በአግባቡ ባይሰነድም ትውልዱ ውሥጥ ጠንካራ ኢትዬጵያዊ ጉራጌነት የዘሩ በማንኛውም ሰዓት ቦታ በኢትዮጵያዊታችን እና በጉራጌነታችን እንድኮራ መስዋት የከፈሉልን ታላቅ የጉራጌ አስተዋይ፣ ጀግኖች አባት እና እናቶች አሉን። 2/3 በላይ ህዝቡ ከተሜነትን (Urbanization) እና ዘመናዊነትን የተዋወቀ ነው። ኢትዮጵያ ተሳካላት ከተባለ ጉራጌን ከተሜ ማድረጓ ነው ልንል እንችላን። ጉራጌው ውለታዋንም ሰፈሬ መንደሬ ሳይል ከተሞቹን ከየአካባቢው ህዝቦች ጋር በመገንባት ይታወቃል።

በየዘመናቱ እየተዋለደ እና እየሰፋ በመምጣት ሂደትም ሆነ ከስርዓቶች መለዋወጥ ጋር የተለያዩ የፖለቲካ አስተዳደር ቅርጾችን በመያዝ ውስጥ አባቶቻችን ‹‹ለጉራጌነቱ ታምኖ›› የኖረ ህዝብ እና ጠንካራ ስብእና ገንብተው ለትውድ አቆይተዋል። ጉራጌው በከተሞች ሁሉ ተሰራጭቶ ኢትዮጵያን ሲያጋምድ የራሱን በጎ እሴት popular culture (ታታሪነትን፣ እድር፣ እቁብ፣ ክትፎ በቆጮን፣ የጉራግኛ የሙዚቃ ስልትትን፣ ቋንቋውን፣ አለባበሱን፣ ቁጠባን፣ ስራ አለመናቅን፣ ጡርና በርቼ፣ እርስ በእርስ መደጋገፍን፣ ዘመን ተሻጋሪ የስተዳደርና የፍትህ ስርአትን፣ መከባበርን....) ለሌሎች ህዝቦች ሲያጋራ፣ ሲጠብቅ እና ከትውልድ እዲሻገሩ ሲያደርግ ኖሯል። የትዮጵያዉያን የጋራ እሴት በማድረግ፤ ከሌሎች ኢትዮጵያዊያን ጋር በመዋለድ፤ የሔደባቸውን አካባቢው ህዝቦች ቋንቋ በመናገር፣ ተግባብተው፣ ባህላቸውን አክብረውና ተቻችለው የሚኖሩ ኩሩ እና ሥልጡን ኢትዮጵያውያን ናቸው።

አሃዳዊቷም ሆነ ፌደራላዊቷ ኢትዮጵያ የተፈተነችበት ቋንቋን፣ ባህልን፣ ሃይማኖት አቻችሎ ማስተዳደር እሴት ለሃገርም ሆለ ለአለም ሃብት በሚባል ደረጃ የጉራጌ ጥንታዊ ህዝብ ካፒታላይዝ አድርጎባቸው ለትውልድ አሻጋግሯል። ዛሬም የተለያዩ ሃይማኖቶች ተቻችሎ መኖር ተምሳሌት በርካታ አብነቶች ያሉት (ዕንኳን ሰዉ ቤተ-ዕምነቶች የተጎራበቱበት) ምድር ነው።

ከላይ ካነሳናቸው በተጨማሪ አሳናሽ ታሪኮችና ሂደቶች በጉራጌ ህዝብ ውስጥ ተከስተዋል። አንዱ ፖለቲካዉ መስክ ከጊዜና ሁኔታ ጋር የሚሄድ ዕራሱንና የሀገሩን ጥቅሞች በመደራደር ማስከበር የሚችል ጠንካራ ተቋም ያልመሰረተ እና በየዘመናቱ የተነሱ መሪዎችና ፖለቲከኞች በችሮታና በደግነታቸው እንዲያኖሩት የፈቀደ

መሆኑ ነው። ሌላው ልሂቃኑ በማያባራ ሽኩቻ፣ ጥርጣሬ ያለመተማመን ውስጥ ያሉ፤ የህዝቡን ሥልጣኔ እና ስነ-ልቦና ደረጃ መርምረው ያልተረዱ፤ እራሳቸውን ለተበታተነ እና ለጥቃት በተመቸ ሁኔታ ውስጥ ለመኖር የፈቀዱ፤ ቀላል የማይባባለው በመጤ በፖለቲካ እሳቤ ቀውስ የሚሰቃይ ነው።

በተለይ ይኼኛው ዘመን ታሪክ ደግሞ በሴራ ፖልቲካ ምክንያት የተፈጠሩ ቢሆኑም አያት ቅድመ አያቶቹ ካቆዩት የከበረ በውስጥና በውጭ አብረው ካሉ ህዝቦች ከባህላዊው አቃፊነትና ከለላነት ወጥቶ ጥራዝ ነጠቅ ግንኙነት፣ አቃፊና ሆደ ሰፊነት የጎደለው፣ ከጥርጣሬ ያልጸዳ፣ በመሰረታዊና በጋራ ጥቅሞቻችን ላይ በመተማመን ያልጎለበተ (የአሸናፊ ተሸናፊ) መሆኑን መተማመን ያስፈልጋል። የአሁኑ የፌደራላዊቷ ኢትዮጵያ ውስጥ መደበኛ ፖለቲካ የተደረገው የዘር ፖለቲካ ሰብአዊነትን በሚደፍቅ ኋላ ቀር መሰረት ላይ የቆመዉ ስረዓት የነኚህ ችግሮቻችን ሁሉ አባት ነው። ሥርዓቱ እንዲ ኢትዮጵያን እንደ አገር ከማዉደሙ በፊት የከፋ መልኩን መግለጥ የሚጀምረው ጉራጌን የመሰሉ መልከ ብዙ ማህበረሰቦችን ማኅበራዊ ስሪታቸውን አፍርሶ ምድራዊ ሲኦል በማድረግ ነው።

ስለሆነም ነው ለአንድ ጉራጌ ይህን ኋላ ቀርና ከሰብአዊነት የተጣላ ሥርዓት መልክ ከማስያዝ የሚቀድም አጀንዳ ሊኖረው አይገባም የምንለው። ይህ ዓይነቱን አነጋገር ብዝሃነትን የማፈን አደጋ ያዘለ አድርገው ሊያቀርቡ የሚሞክሩ ሰዎች አይጠፉም ይሆናል። ነገር ግን እነኝህ ሰዎች ኮሚኒስቱ ስታሊንም ሆነ ሊበራሉ ዊልኪምሊካስ ለብዝሃነት አያያዝ ከመፈላሰፋቸው ብዙ መቶ ዓመታት ቀደም ብሎ የጉራጌ ሰው በአኗኗሩ ለጥያቄዎቹ መልስ መስጠቱን ልናስታውሳቸው የሚገባው። ሴረኞቹና ተላላኪዎቻቸው ‹‹ጉራጌነትን›› በፖለቲካ የተፈጠረ ማንነት አድርጎ በመመልከት ያንን ታላቅ ማንነት ሲከፋፍሉ ኖረዋል። ከዉጫዊው ወያኔና ተከታዮቹ ሃይሎች በተጨማሪ ጥቅመኛ የዉስጥ ፖለቲከኞች የሚዘሯቸው አጀንዳዎችን፣ የኢ-ፍትሃዊነት እና የኢ-እኩልነት እክሎች ለዚህ ጉራጌነትን የመከፋፈል ተግባር መሳርያ ሆነው አገልግለዋል።

ከ2010ሩ ህዝባዊ ለውጡ መምጣት ማግስትም ቢሆን የተጠበቁ ሪፎርሞች ለህዝባችን ችግሮች መፍትሄ ከመሆን ርቀዋል። ችግሮቻችን እንደውም ተባብሰው ቀጥለዋል። በፖለቲካው መድረክ እንደ ጉራጌ ህዝብ በዋና ዋና ጥያቄዎቻችን (አጀንዳዎቻችን) ጥርት ያለ ወጥ አቋም መያዝና መግባባት ይጎድለናል። ለአብነት፡-

1) የጉራጌም ሆነ የኢትዮጵያ ህዝብ ችግሮች ሁሉ እናት የሆነው ህገ-መንግስት እንዲሻሻል ማድረግ ጉዳይ፤
2) የፌደራል ስርዓቱ የክልል መንግስታት አወቃቀር በተገቢው አጢኖ ያለመፍታት እና ራስን በራስ የማስተዳደር የጉራጌ ክልልነት ጥያቄ ተፈጻሚነት ጉዳይ፤

3) ከዞኑ ውጭ ያሉ ጉራጌዎች የሰቆቃ ኑሮ አያያዝ ጆሮ መነፈግ እና ጉራጌዎች መብት መከበርና ህጋዊ ውክልና ጉዳይ፤
4) ፍትሐዊ የልማት ተጠቃሚነት የሚጋግጥ አሰራር ለዘለቄታው (የህግ ማዕቀፍ) ያለመኖር ጉዳይ፤
5) በዉስጥ ያሉ የህዝቦች የአደረጃጀትና የአስተዳደር ጥያቄዎች፣ አፈታት በህዝቡ የእርስ በእርስ ግንኙነት ማስተክከል... የሚሉት ዋነኛዎች ናቸው፡፡

ለአመታተት ወደ ቀውስ ወስደውን፤ ለለውጡ መምጣት ምክንያት የሆኑ የፖለቲካ፣ የኢኮኖሚና ማህበራዊ ችግሮች ገንግነው፤ የነበረዉ ማህበራዊ ሥምምነት በመዳከሙ፤ ከዚህ በፊት በተወሰነ ደረጃም ቢሆን የህዝቡን ሰላምና መረጋጋት ጠብቀው የቆዩ ተቋማትና ልምዶች ከጠቅም ዉጪ እየሆኑ በመሄዳቸው በማህበረሰባችን ውስጥ ከፍተኛ መዋዠቅ ተከስቷል፡፡ ሥምምነትም ጠፍቷል፡፡ አስማሚና አቅጣጫ ጠቋሚነት ተዳክሞ ይገኛል፡፡ በህዝቡ የሚነሱ ጥያቆዎችን ያነገቡ፣ የትግላችንና የብሄርተኝነታችን ምሰሶ የሆኑ ጤናማ የህዝብ እንቅስቃሴዎች ከአላማቸዉ ዉጪ ጥቂት በማይባሉ አካላት (አክቲቪስቶች፣ ፖለቲከኞች) ተጠልፈው በህዝብና በለውጥ ስም ለልዩ ልዩ ትናንሽ ፍላጎቶች ማስፈጸምያ ሆነዋል፡፡ እነዚህ፡- ሆን ብለው በጥላቻ በታወሩ፣ በስሜትና በትናንሽ ጥቅም በሰወራቸው እና ባለማወቅና በመንገኝነት ነው፡፡ በመስዋትነት የወደቁ ወንድሞቻችንን እና የጉራጌን ህዝብ ክብር በሚነካ መንገድ ተጉዘው ካለፈዉ የባሰ ችግር ውስጥ ጥለውናል፡፡ ቆም ብለን ካልተፈታተሸን እነዚህ መንገዶች ደሞ የትም የማያደርሱን ናቸው፡፡

## 4) የጉራጌ የፖለቲካ አስተላለፍ፤ የጉራጌው የፖለቲካ ትግል እና ብሔርተኝነት

የጉራጌው የፖለቲካ ትግል በኢትዮጵያ የፖለቲካ ውስጥ ባመዛኙ ሰው ዘንድ የቀኝ ዘመም የፖለቲካ ብያኔ ይሰጠዋል፡፡ ቀኝ ዘመም የሚባሉት በጥቅሉ የግዛት አንድነት (Republician)፤ የባሕል እና ወግ አጥባቂዎች ነው፡፡ ጠንካራ መንግሥት፣ የሥልጣን ተዋረድ እና ስርዓት ተኮር መለያቸው ነው፡፡ እዉነት ነው ጉራጌው በአመዛኙ በሐገርና በግዛት አንድነት (መካለልን ጨምርሮ) ጉዳይ ላይ የአባቶቹ የፊታውራሪ ሃብት ጊዮርጊስ ዲነግዴ፤ የደጃዝማች ባልቻ ሳፎ፤ ደጃዝማች በቀለ ወያ፤ ራስ ደስታ ዳምጠው፤ ጀነራል ወልደ ስላሴ በረካ፤ ጀነራል ይልማ ሺበሺ እና ጀነራል ተስፋዬ ሃብትማርያም ወራሽ፤ ወግ አጥባቂ (conservative) የፖለቲካ አቀንቃኝ እና ኢትዮጵያዊ ብሔርተኛ ነው!! ነገር ግን በግለሰብ መብት፣ በሃየማኖት እና በብሔር እኩልነት መከበር ጉዳይ፤ በልማትና ብልፅግና አጀንዳዎች በአካታችነት ረገድ ከዘውግ-አሃዳውያን (የጎሳ ፖለቲከኞች) የተሻለ ተራማጅ አመለካከት ያላቸው ናቸው፡፡ ይህ እውነታዉም ብያኔውን ወደ መሐል ፖለቲካ የቀረበ

መሆኑን የሚያስረዳ ነው። ያ ማለት ልሂቃኖቻችን ለግል ነጻነታቸውንም፣ ለቡድን ክብራቸውንም ሁለቱንም የሚታገሉ ናቸው ማለት ነው። ብዙኀን ከግራ ወደ ቀኝ እንደግል ምርጫቸው ሊዋልሉ ይችላሉ ብሎ መበየንም ይቻላል። የግል ነጻነታቸው የበለጠ የሚጠቅማቸው ጉዳይ ላይ ስለ ግል ነጻነት ይከራከራሉ፤ የቡድን ክብራቸው የበለጠ የሚጠቅማቸው ቦታ ላይ ስለቡድን መብቶች እና ጥቅሞች የመክራሉ። መሐሉ በአጭሩ የማመቻመች (compromise) መስክ ነው የምንገኘው።

ዘመናዊት ኢትዮጵያ ታሪኳ ዘመነ መሳፍንትን የሰነበተ መከፋፈል ዘግታ ለአንድነቷ (Reunification) የባጀችበት ነው። ይህም ምእራፍ በጉልበትና በብልሃት የተፈጸመ፣ ያላለቁ እና ወደ እዚህኛው ትውልድ የተሸገሩ የቤት ስራዎች ያሉነት ነው። በአጤ ምኒሊክ ከ1867 እስከ 1883 ወደ ጉራጌ የተደረገው መስፈፋፋትና ዘመቻም ከፊሉ በሰላም ከፊሉም በኃይል የተጠናቀቀ ነበር። ጦርነቶቹ ጥንኬሬ ንጉሰ ነገስቱን የእራሳቸው የአውደ ውጊያ ተሳትፎ ትግል ጭምር ጠይቋቸው ነበረ። ህዝቡ የከፈለው መስዋትነት እና ከጦርነቱ መጠናቀቅ በኃላ ከሁለቱም ወገን መሪዎች የወሰዷቸው ፈጣንና አወንታዊ እርምጃዎች ታግዞ የጉራጌ ህዝብ በኢትዮጵያ በሃገረ መንግስት ግንባታ፣ የዘዋሬን ኢትዮጵያ ለመፍጠር የማይተካ ሚና የተጫወተ እና ጉራጌውንም የዛሬውን መልኩን እንዲይዝ እንዳስቻለው በብዙ ማስረጃ ማስረገጥ ይቻላል።

የጉራጌ ልሂቃን በየዘመናቱ የነበረውን ‹‹አግላዩ›› የኢትዮጵያ የፖለቲካ ባህልን ተቋቁመው፤ እራሳቸውን ከማግለል ቆጥበው እና የኢትዮጵያዊ ብሔርተኝነት ፖለቲካ ምሰሶ ሆነው በፅናት በመቆምና በመታገል ረገድ ዛሬም ድረስ ከፋና ወጊዎቹ ተርታ ያስመድባቸዋል። በርግጥ ከትናንት ያልተማረው፣ ዛሬን ያልዋጀው እና ነገን አሻግሮ ማየት ተስኖት የሚዳክረው ቆሞ ቀሩ የኢትዮጵያ ፖልቲካ የጉራጌ ማህበረሰብ ዘመናዊት ኢትየጵያን በማቅናቱ ታሪክ የነበረውን ሚና በአጼዎቹ፣ በደርግና በኢሕአዴግ እንደሆነው ሁሉ በብልፅግናም እደደበዘዘ መቀጠሉን መረዳት ተገቢ ነው። ይም ሆኖ ልሂቃኑ ዛሬም ሆነ ትላንት ጉራጌ ውስጥ ኢትዮጵያ ጠል ፖለቲካ ካራመዱት ጋራ ይሆንል እንጂ ከኢትዮጵያ ጋር ከወገኑ ከየትኞቹም መሪዎችና ፖለቲከኞች ጋራ የጋራ የፖለቲካ አጀንዳ ከመቅረጽና ከመታገል በዝነው አያዉቁም።

በንጉሱ ዘመን መሬት የረገጠውን የብሔር ጭፍለቃ በመቃወም፣ ለእኩልነትንና ለፍትህ በመፋለሙ ረገድ በኢትዮጵያ ተማሪዎች እንቅስቃሴ ከዘመን ተጋሪዎቻቸው ወጣቶች ጋር ተሰልፈዋል። ማእከላዊ መንግስቱን በህዝቡ ላይ የሚያደርሰውን በደል በመቃወም ከህዝቡ የወጡ የተማሩ ልጆች በዩንቨርሰቲ መምህራን ማህበርና በሌሎች ንቅናቄዎች ውስጥ በመግባት ጉልህ ሚና ተጫዉተዋል። በየዘመናቱ ትልቁን የጉራጌ

ማህበረሰብ ከአስከፊ ጭቆና እና ጨቋኞች ለማላቀቅ፣ ከበደል ለመታደግ፣ የወደቀ ማንነቱን ለማንጻት የደፈሩ ተወላጆቹ ከከተሞች እስከ አገር ቤት፤ እንዲሁም ከሌሎች ኢትዮጵያዊያን ወንድሞቻቸው ጋር በረሃ የዘለቀ የትጥቅ ትግል ተጋድሎ ፈፅመዋል። መሬት ላራሹን እንግበው፤ ለመሰረተ ትምረትን ዘምተዋል። በርካቶች በኢህፓነት ተመንጥረው ስለሃገራቸውና ስለህዝባቸው የስቃይና የሞት ጽዋን ተጎንጨተዋል።

የኢትዮጵያን ምሰሶ የመነቅነቅ ፖለቲካ ጥያቄዎችን አለማንሳታቸው ሐጥያት ነው ካልተባለ በቀር ከአስራ ዘጠኝ 30ዎቹ፣ 40ዎቹና 50ዎቹ ጀምሮ በሁለቱ የጃንወይ ጀነራሎች (ጀነራል ይልማ ሺበሺ እና ጀነራል ወለወደስላሴ በረካ) ፊትአውራሪነት የጉራጌ ልጆች ቀደምቱን የፖለቲካ ጥያቄ በማንሳትና በከተማና በገጠር ያለውን መላውን የጉራጌና የዙሪያውን ህዝብ ጭምር ያነቃነቀና ያሳተፈ ‹‹በራስ አገዝ ስልት›› ማህበረሰብን የማልማትና የማንቃት ታልቅ ተጋድሎ ፈፅመዋል። ህዝብ አደራጅቶ በራስ አቅም መገዶችን (ከአለምገና - ቡኢ- ቡታጅራ - ሆሳእና - ወላየታ ሰዶ እና ከወልቂጤ ጀምሮ ሁሉንም የሰባት ቤት ጉራጌ ወረዳዎች የሚስተሳሰር እና ሆሳእና የሚዘልቅ መንገድን) አሰርተዋል። ደራሲ ገ/እየሱስ ኃ/ምርየም ‹ህብረት ስራ› በሚለው መፃፋቸው መንገዶችን ከመገንባትም ባሻገር፣ ለህብረት ስራ እሳቤዎች መሰረት በመሆን፤ የክፍያ መንገድ ስርዓት በመተግበር፣ መንገዶቹን በቋሚነት የማስተዳደርና ዘላቂነ አገልግሎት እንዲሰጥ በማስቻል ቀዳሚ መሆናቸውን ዘግበዋል። ትምህርት ቤቶችንና ሌሎች የልማት እንቅስቃሴዎችን በመገንባትና በመደገፍ ገጠርን የማልማት ባህል አርአያ በመሆን ኢትዮጵየዊና አፍሪካዊ ፈር ቀዳጅ ብርሐን ለኩሰዋል። ይህ እንቅስቃሴ ንጉሱም ሆኑ ደርግ ፖለቲከኞችና መሪዎችም እንደፀጋ ተመከው ታላቁን ህዝባዊ ሕልም በሚገባ ደግፈው ለፍፈሬ አብቅተዋል ባንል እንኳ ለማደናቀፍ ያለመሞከራቸውን እንመሰክራለን። በነገራችን ላይ ይህን የመጀወሪያው የጉራጌ ልጆች እንቅስቃሴን የሚገዳደር በጉራጌ ፖለቲካ እና የልማት ተሳትፎ መነቃቃት ትልቅ አሻራ ማሳረፍ የቻለ ማህበረሰባዊ ንቅናቄ ዛሬም የለም።

በኢትዮጵያ የንድነት ፖለቲካ በራሱ ልሂቃን ተራማጅ ባህርያት መዓደል እና በማይተኙልን የዉጭ የጠላቶቻችን ሴራ ተዳክሞ የብሄር ፖለቲካና ፖለቲከኞች የሃገሪቱን የፖለቲካ አውድ ከተቆጣጠሩ ዋዜማ ጀምሮ አክራሪ ብሔርተኛነት መንግስታዊ ተቋማትን ተቆጣጥሮ ዘር ተኮር አሰራሮችን መዋለድን ተከትሎ ውስን የጉራጌ ልሂቃን ጉህዲግ (የጉራጌ ህዝብ ዲሞክራሲያዊ ድርጅት) ሰኔ 1983 ዓ.ም እንዲሁም በሀምሌ ወር 1983 ሶጎህዲድ (ሶዶ ጎርደና ህዝብ ዲሞክሳሲያዊ ድርጅት) በተከታታይ መስርተው እንቅስቃሴ ጀመሩ። እነዚህ ድረጅቶች ታሪካዊ የቤተ ጉራጌ ግዛት አካል ሆነው የቆዩትን (የጨቦና ጉራጌ እና የሐይቆችና ቡታጅራ

..ወዘተ) ግዛቶችንና ህዝቡን ማንነትና አንድነት ለማስጠበቅ፤ ታሪካዊ የአዲስ አበባና የጉራጌ የግዛቶች ጉርብትና ለማስከበር ከነጉድለታቸውም ቢሆን ትልቅ ዋጋ ከፍለዋል። ሁለቱ ድርጅቶች በቅርበት በጋራ ይሰሩ የነበረ ሲሆን ሶጎህዲድ በጉህዲድ ውስጥ ተወካዮች ነበሩት። የጉህዲድ ምክር ቤት 2 ተወካዮቹን ለሽግግር ምክር ቤት አባልነት ያሳተፈ ሲሆን ዶ/ር ፍቃደ ገዳሙ የሽግግር መንግስቱን በምክትል ፕሬዝደንትነት እስከማገልገል ደርሰው የነበረ ቢሆንም የሽግግሩ ቁማር ሰለባ ሆነዋል። እንግዲህ የፖለቲካ ድርጅት መስርተው ለጉራጌው ህዝብ ጥቅም በመሞገት ቀዳሚዎቹ የጉራጌ ብሄርተኞች ጉህዲድዎች ናቸው ማለት ነው። ኢህአዴግ እነዚህ ፖለቲከኞች እንቅስቃሴ ያልተዋጠለት በመሆኑ ዙፋኑ እየተደላደለ ሲመጣ ድርጅቶቹ ላይ በትሩን የበለጠ አሳርፎ የከፋፍለህ ግዛዉ ሰለባ አደረጋቸው። ተዳክመው እንዲበታተኑ ወጥኖ አሳካው። የህዝቡን ጥያቄዎች ያለ ሁነኛ ሞጋች አስቀርቶ እንዳሻው አደረገ።

ታምራየው ሲማ፤ የጉራጌ ህዝብ ማንነት በኢትዮጵያ አንድነትና ነጻነት (ዕቅፍ ውስጥ) በሚል ርዕስ 2014 ዓ.ም ለህትመት ባበቁት መጽሃፋቸው የ1983ቱን ሽግር ሂደት ሲያሰታዉሱ ‹‹ ኢህአዴግ ትንሽ ሰነባበብቶ ያለምንም በቂ ምክንያትና መግለጫ የደቡብ ኢትዮጵያን ከ50 በላይ የሚሆኑትን የተለያዩ ጎሳዎች ቢሆኑም የደቡብ ብሔር ብሔረሰቦች እና ህዝቦች ብሎ በአንድ የአስተዳደር መዋቅር ስር ጨፈለቃቸው። በዚህ ሁኔታ ደግሞ አገሪቱ አስራ አራት ከነበሯት ክፍለ ሀገራት ወደ ዘጠኝ አወረዳቸው። አምስት ክልሎች ከነበሩት የደቡብ ኢትዮጵያ ክልሎች ወደ አንድ ክልል የጨፈለቃቸው ያኔ ነው። ይህም በመሆኑ ውሎ አድሮ የጉራጌ ህዝብ እንደተቀሩት የደቡብ ህዝቦች ያለአግባብ የተነጠቀውን የአስተዳደር ደረጃው ተመልሶለት ራሱን ማስተዳደር እንዲችል በህገ መንግስቱ መሰረት የክልልነት ደረጃ እንዲፈቀድለት አግባብ ባላቸው የመንግስት ባለስልጣን መስሪያ ቤቶች በነውጥ ያልታጀበ ሰላማዊና ህጋዊ የሆነ ጥያቄ ሲያቀርብ ቆይቷል። ይህም በጉህዲግ የግባር ፕሮግራም ላይ ይገኛል።›› ሲሉ አስፍረዋል።

በኢህዴን/ኢህአዴግ ውስጥ ጉራጌ ብሄር ድርጅት እንዲመሰረት ከድል በኃላም የራሱን አደረጃጀትና ክልል መመስረት አለበት ያሉ ታጋዮች እና የመለመሏቸው ጥቂት ወጣቶች፤ ጉህዲንንና ሶጎህዲድን ለማፈራረስና የህዋት ከፋፍለ ግዛዉ መሳርያ ሆነው ያባከኑት ሕዝባዊ አንድነትና ትግል እንዳለ ሆኖ ህወሃት ነብስዋን ይማረውና እነኝህን ከ300 የሚልቁ (የጉራጌ፣ የስልጤ፣ የማረቆና የቀቤና) ታጋዮች ጉዞብዴን (የጉራጌ ዞን ብሔረሰቦች ዲሞክራሲያዊ ንቅናቄ) ስር ተደራጅተው ጉራጌው እራሱን በራሱ የሚመራበት ክልል ሆኖ እንዲደራጅ የተወሰነ ትግል አድርገው በህዋት ጌቶች ተሸንፋዋል። እነኚህ ታጋዮች አንድም ማባበያ

የቀረበላቸው የመላው ደቡብን ትግል እንድያስተባብሩና እንዲመሩ የቀረበላቸው ጥያቄ አማሏቸው፤ ሁለትም ዉሎ ሲያድር ሀገር ያለተቀናቃኝ እጃቸው እንደወደቀች በገባቸው እና ጉራጌ ህዝብን ከጫካ እስከ መንግስትነት ዘመናቸው በጠላትነት በሚመለከቱት አለቆቻቸው በሚወረውሩላቸው አጀንዳዎች እና ሴራዎች ተከፍለውና ተዳክመው እርስ በእርስ ተጠፋፉ። ህዝቡንም የጅብ እራት አደረጉት።

ለዘመናት ተስፋ አድርጎ ከሁሉም ኢትዮጵያ ህዝብ ጋር ጉራጌው የታገለላቸው የፖለቲካ፣ የኢኮኖሚና የመህበራዊ ልማት ጥያቄዎች እንደ ጉም ተነኑ። በጉራጌ ህዝብ ላይ የሚደረገዉ ግፍ እና ሰቆቃ ተባብሶ ቀጠል። ጥቃት ሲባል ለአንዳንዱ ሰዉ መታሰር እና መገደል ወይም መሰድድ ብቻ ይመስለዋል። ይህማ በባለፉት 27 አመታት ከሞላ ጎደል በሌሎች ብሔረሰቦች ላይም ደርሷል። የጉራጌ ግን የተለየ ነዉ። የጉራጌ ጥቃት በህገመንግስቱ፤ በፌደራሊዚሙ፤ በፖሊሲ እና በተቋማት (Institutionalized) የተደረገና የተደገፈ ነዉ። ህወሃቶች ሁሌም አንድ የሚያስቡት ወሣኝ ነገር ስልጣን ነው። ሊገዳደረን ይችላል ብለው ያመኑትን ኃይል ሁሉ ያለ ርህራሔ ያጠቁታል። በ1983 ጉራጌ በቁጥር ማጆሪቲ ህዝብ ነበር በክልሉ ውስጥ። በመሆኑም ጉራጌን አካባቢ ወደ ትንንሽ ዞንነት በመሰነጣጠቅ በክልልና ፓርላማን ወንበር የአካባቢውን የላይነት በመንጠቅ የጉራጌ ምድር ህዝቦችን በመከፋፈል እነሡ የጥላቻ እና የበቀል የድል ፅዋ ተጎነጩ። በሀገራዊ ህዝብ ቆጠራ የጉራጌውን አሃዝ በማሳነስና ከብሔራዊ ጠቅም አጀንዳዎች ለመግፋት ከቆጠራ ሂደት እስከ መረጃ መተንተን የተፈፀመው ነውር አጀኢብ የሚያሰኝ ነው። በዲኤን-ኤ የተገመደውን ህዝብ በቋንቋ/ዲያሌክት ትንሽ ልዩነት ብቻ ጠላትነት ሠብከው ለያዩት። በዚህም ያለምንም ፓወር እና አነስተኛ በጀት ብቻ እየተመደበ ጠፍጥፈው በሠሯቸው ምስለኔዎች ህዝቡን በመንደር ከፋፍለው እያባሉና እያጋደሉ ኖሩ።

ህውሃት ‹‹ያለኢኮኖሚ የበላይነት የፓለቲካ የበላይነት›› እንደማይመጣ ቁልጭ አርጎ የጻፈና ያስፈጸመ ነውረኛ ድርጅት ነው። እንግዲህ ኢትዮጵያ ውሥጥ 27 አመት ምን አይነት መንግስታዊ ሌብነት በህዋትና አጋሮቹ እንደተፈፀመ አውርተን አንጨርሰውም። ይህ ሁሉ የሚሆነው ታድያ ሌላው ህጋዊ ነጋዴ ከንግድና ከማምረት ስራው በተደራጀ እና በውስብስብ መንገድ በተሠሩ አሻጥሮች በግፍ እንዲከሥርና ከገበያ ውጭ እንዲሆን እየተደረገ ነው። በንግድ ውድድር አሻጥር ሆነ ተብሎ ጉራጌን የሚጎዳ አሰራር ፖሊሲ ተግባር ላይ ውሏል። ጉራጌው ከቆረቆራት መርካቶ ባዶ እጁን አጨብጭቦ ወጥቷል። የጉራጌውን ህዝብ በከፍተኛ ታክስ አሰባሰብ ሂደት በዘመናዊ መልኩ የሚበዘብዝ ስርአት ተዘርግቶ ገቢራዊ ሆኗል። በከተሞች ማስተር ፕላን፣ መሰረተ ልማት ዝርጋታ እና ከተማ ማዘመን ሰበብ ጉራጌው ከመሰረታቸውና አሻራውን ካኖረባቸው የሃገሪቱ ከተሞች

ማፈናቀልንና ለማደህየት በህወሃት አጋፋሪነት በያካባቢው ጽንፈኛ ካድሬዎች በገዛ ክልሉ ውስጥ ባሉ ከተሞች ጭምር ተፈጽሞበታል። በየከተሞቹ ጉራጌው የእሳት እራት የሆኑበት የንግድ ሱቆችና ድርጅቶች እሳቱ እንደፖለቲካው ጉራጌዎቹን መርጦ እንዳላነደዳቸቸው ሚያሳምነን ጭብጥ ከቀረበ ደስ ይለኛል።

የጉራጌ ህዝብ የህልውና መሰረቱን መነጠቅ የስርአቱ የማያቋርጥ አጀንዳ ሆኖ ቀጠለ። ለብሄር መብት ቆሜያለው በሚለው ድርጅት ጉራጌ ተጨቁኖ የኖረ መሆኑን ክዶና ለአመታት ውድ ልጆቹን ገብሮ ለፖለቲካዊ ለማንነቱ መታገሉን አንሸዋሮ ቸርቻሪውን ሁሉ እንደ ፊዉዳል አሳደረ እና በዝባዥ ማሳደድ መንግስታዊ ስራ ሆነ። ሌላው ብሄረሰብ ለይስሞላም ቢሆን የተፈቀደው የብሄር መሰባሰብ ለጉራጌው ሲሆን ሃጥያት ሆነ። የጉራጌን ህዝብ አንድነቱን እና አብሮነቱን መጠበቅ ባህሉን፤ ቋንቋዉን፤ ትዉፊቱን እና ሌሎች ማህበራዊ እሴቶችን ማዳበርና እራሱን እንዳያበለጽግ ብሎም ለኢትዮጵያ ሀገሩ በተደራጀ መልኩ የሚጠበቅበትን እንዳያበረክት ተደረገ። ይሄ የብሔር ተኮር ጥቃት ‹‹የጉራጌው የብሄርተኝነት ትግሉን›› አስገዳጅነትና የሕልውና ጉዳይ በመሆኑ በብሄር ጥላ መሰባሰቡን አማራጭ አልባ አደረገው። ይሄ ህገመንግስታዊ እና ተቋማዊ ጥቃት ለማምከን ካለው የመታገያ አውድ ውጭ ሌላው በሙሉ ተከርችሟል። ይህ ውስጥ ውሰጡን ሲብላላ የከረመ እዉነትና ብሶት ብዙሃኑን በተለይም ወጣቱን እያሰባሰበና በጉራጌው መደራጀት ላይ የሚደረገውን አፀፋዊ ምላሽ እየተጠናከረና የበለጠ ህዝባዊ ድጋፍ እያገኘ መጣ።

የጉራጌ የአዲስ አበባ ባለቤትነት ጉዳይ ‹‹ከኃላ የመጣ አይን አወጣ›› ሆኖ እንዲህ በአማራና የኦሮሞ ልሂቃን የብቻቸው መሻኮቻ ከመሆኑና የሌሎች ብሄረሰብ ልሂቃን በሸገር ጉዳይ የአጃቢነት ሚና ብቻ እንዳላቸው አምነው ከመቀበላቸው በፊት የስፍራው ቀደምት ባለቤቶቹ ጉራጌዎችና ወርጂዎች መሆናቸውን በብዙ ማስረጃ መሞገት ይቻልል። ይህንን እውነት ታሪክ ማስረጃዎችን ተቅሰን ብንሞግት ‹‹እኔም አራዳ አንተም አራዳ ምን ያጣላናል በሰው በረንዳ›. ተባብለለው የሁለቱም ዘውግ ልሂቃን ይሻረኩ ይሆናል። በነገራችን ላይ እራሳቸው ለዚህ ሙብግት የሚዘረዝሩት ማስረጃ ብቻ የኛን ነባር ባለቤትነት ያስረግጥልናል። ታሪካዊው የጉራጌን ሙሉ በሙሉ ከዲስ አበባ ፖለቲካ የማስወጣት ስራ የተሰራው የህወሀት ኢትዮጵያ ጠልነት ኑፋቄ አዲስ አበባን በህገ መንግስቱ አንቀፅ 49 አዲስ አበባ በኦሮሚያ ክልል መሀል የሚገኝ ንብረት አድርጎ ሲያውጅ ነው። የጉራጌውን ከአዲስ አበባ የግንኙነት ማእከሉ መቁረጣቸውን ነገር በፖለቲካም በህግም አፀኑ። ህወሃት አዲስ አበባ ተደላድላ ለመቆየት ለጊዜው ሸገርን በዚህ መንገድ ለነሌንጮ ከመስጠትና ድጋፋቸውን ከማግኘት የተሻለ አማራጭ አልነበራትም።

ሰባ ከመቶ የሀገሪቱን ንግድ በመቆጣጠር የኢኮኖሚው ምሰሶ በሆነችው ከተማ ኢኮኖሚውን በአመዛኙ ታታሪዎቹ የጉራጌ ልጆች ይዘውሩታል። የመጨረሻው የህዝብና ቤት ቆጠራ፣ ከአዲስ አበባ ነዋሪዎች መሃል 47% ዐማራ፣ 19% ኦሮሞ፣ 16% ጉራጌ፣ ቀሪው የሌሎች የኢትዮጵያ ብሔር ብሔረሰቦች መሆናቸውን ይናገራል። ነገር ግን የፖለቲካ ስልጣን ክፍፍሉ ከአሃዝና እውነት ከዚህ ፍፁም ያፈነገጠ እና ጉራጌውን ያገለለ ነው። ይህ የፈጠጠ ሃቅ ላይ ቆመን 4 ኪሎን የተቆጣጠሩት የአባገዳ ልጆች ደግሞ ‹አዲስ አበባ የኦሮሞ ናት› የሚለውን ትርክት ጉራጌዎች እንድንቀላቀል ሰንገው ይዘውናል። በከፊልም ቢሆን ተሳክቶላቸዋል። በምርጫ ዋዜማ በነበሩ ተደጋጋሚ መድረኮች ክልሉንና ዞኑን የሚያስተዳድሩት መሪዎች በኩል በቀጥታ ‹አዲስ አበባ› የኦሮሞ ናት ይህን መቀበልና መደገፍ አለባቹ የሚል መልክት ለህዝቡ በሃላል ተነግሯል። እነርስቱን ጉራጌ ‹ይሸጣል› ሲባል መቀመጫውንም ነው እንዴ እስክንል ድረሰረ ታዘብናቸው። የጉራጌ ባለሐብቶችን እና ታዋቂ ግለሰቦችን ሰብስቦ ማስጠንቀቅ በሉት ማባበሉ ለጉድ ነው። በነገራችን ላይ በአፍሪካና በኢትዮጵያ የመጀመሪያዉ ‹‹የራስ አገዝ ልማት›› ተምሳሌቱ ‹‹የጉራጌ ልማት ባህል ማህበር›› ከተመሰረተባትና ዋና ፅህፈት ቤቱን በህዝብ ገንዘብ ከገነባበት ሸገር ህዝቡ መሃል ተቀምጦ ገጠሩን ያልማ በሚል ውሃ በማያነሳ አመክንዮ ተገፍቶ አገር ቤት የመግባቱ ቁማር ነው። ለኦህዴድ መገበራችን ከዚህ እንኳን አያድነንም እንዴ ጎበዝ? ተነቅለን አለቅን እኮ!?

ይባስ ብሎም የ2010 የለውጥ ተስፋችን ትግሉ ፍሬ ሳያፈራ ቅሪቶቹና ወራሾቹ በተረኛነት መንፈስ ላለፉት 4አመት እየተጓዙበት ያለው የፉክክርና አክራሪ ብሄርተኛ መንገድ ብሔርተኝነቱን እየመገበ አፋፋው። የተደቀነቀብን ህዝባዊ አደጋም ጭራሽ ተባብሶ አሁን ወደ ደረስንበት እጣ ፈንታችን ለማወቅ እንኳ እድል ወደ ማይሰጥ ደረጃ ደረሰ። የዚህ የለውጥ ትግል ምእራፍ ትልቁ ስራ የሆነው ሕወሃትን እና የአፓርታይድ አጀንዳ ማስፈፀሚያዋ የነበሩ ተቋማት institutions መቀየርና ለውጡ ለተነሳበት cause የሚበጁና የሚስማሙ አድርጎ ማስቀጠል መሆኑ መረሳት፤ ለውጡ በአክራሪ ብሄርተኞች እጅ መውደቁ ያሠጋው ህዝብ በባለፉት አራት አመታት እንዳየነው ሕወሃት ያስተዋወቃቸዉ እና ሀገሪቱ ለባለፉት 30 አመታት ስትገዛባቸው የቆዩ መደበኛ እና ኢ-መደበኛ ተቋማትን ተቀብሎ የራሱን ጥቅም ለማስኬድ እንዲሁም እራሱን የማይመስለዉንና የማይመቸውን በማስወገድ ለማስቀጠል የሚንደፋደፍ ቡድን፤ ተቋም እና ግለሰቦች በይፋ መኖራቸውን ያየ ህዝብ ለብሄርተኝነቱ ይሁንታ እየሰጠ ብሄርተኝነቱን ትግል ህዝባዊ መሰረት አስያዘው።

ለማንኛውም ዛሬ ከነኚህ ገፊ ሁኔታዎች ተነስቶ የእኛ የጉራጌዎች የአመታት የፖለቲካ ትግልና ብሔርተኝነት የጉራጌ ህዝብ እና የኢትዮጵያ አንድነት በማስጠበቅ ለመጪው ትውልድ ማንነቱን፤ ባህሉን እና ማህበረሰባዊ እሴቶቻችን ሳይሸራረፉ እንዲተላለፉ ማድረግ እንዲሁም ብልጽግናውን ማረጋገጥ አላማው አድርጎ መሰረቱን አደላድሏል።

የጉራጌው ትግል የጉራጌ ልጆች ከማህበረሰቡ ሲወርድ ሲዋረድ የተቀበሉትን ማንነት እና እሴቶች በማበልጸግ ልክ እንደ ትናንቱ የወደፊት ራእይ እንዲኖረዉ በማድረግ ከጉራጌ ህዝብ አልፎ ለኢትዮጵያና ለአለም የቢዝነስ፤ የሳይንስ፤ የቴክኖሎጅ፤ የስነ ህንጻ፤ ኪነ ጥበብ እና የባህል እምቅ ሃብቶችን በማበርከት አለምን ለነዋሪዎቿ ምቹ ማድረግ ነዉ። የማህበረሰቡን ሞራል እና እሴት ያላከበረ ትዉልድ አላማ አይኖዉም። ከራሳችን ታሪክ እንደተማርነው ባህሉን ቋንቋዉን እና ማንነቱን የማይንከባከብ የማያሳድግ ማህበረሰብ ነጋዴ፤ መሪ፤ ሳይነቲስት፤ አስተማሪ፤ ሃኪም ሊያፈራ አይችልም። ቢያፈራም ለአገር ሸክም ይሆናሉ እንጅ አይጠቅሙም።

ወቅታዊው ትልቁ ‹‹የክልል ምስረታ›› ጥያቄያችንም ከህዝባዊ ትግሉ ተነስቶ በህዝባዊ ምክር ቤቶቻችን ጸድቆ ምላሽና ይሁንታ የሚጠባበቀው አጀንዳችን በሀገሪቱ በየጎጡ እንደሚታዩት የፖለቲካ ጥያቄዎች ትናንሽ ራእይ፣ የተበድለናል ለቅሶ፣ ወይንም ፍርጠጣ ያነገበ አይደለም። የጉራጌ ህዝብ የአመታት የፓለቲካ ትግል ለዚህም ነዉ ተጎድተናል ወይም ተጠቅተናል የሚል ትርክት ብቻ ላይ ያልተንጠለጠለ ነዉ የምንለው። ተጎድተናል ወይም ተጠቅተናል የሚል ትርክት ላይ ብቻ የተንጠለጠለ ቢሆን ኖሮ ልክ እንደሌሎች ብሄርተኞች ያ-ህዝብ ጠላታችን ነዉ፤ ለማጥፋት መነሳት አለብን ስንል እና አዳዲስ ጠላት ስናፈራ ውለን እናድር ነበር። የጉራጌ ብሄርተኝነትን ልዩ የሚያደርገዉ የህዝቡን የአመታት የፓለቲካ ለመመለስ በዚህ አይነት ዘላቂ መፍትሔ ላይ ያተኮረ እና ታላቅ ራእይ የሚመራ መሆኑ ነዉ።

የጉራጌ ብሔርተኝነት ስርዓቱ በፈቀደልን ሜዳ ለመሰባሰብ እና ከተሰባሰብን በኋላ ደግሞ ወደ ትክክለኛው ዓላማችን እንሸጋገርበታለን የሚለው የብዙሃኑ ስሜት ነው። ህዝቡ ሆ ብሎ የደገፈው ለመሰባሰብ እራስን ለማዳን ሌላ አማራጭ በመጥፋቱ ነው። የጉራጌን ብሔርተኝነትን ህዝቡ በወቅቱ የተቀበለው በዚህ መልኩ ነበር ነገር ግን አንዳንድ የፓለቲከኞችና አክቲቪስቶች አንድም የትግሉን ይዘትና መዳረሻ በቅጡ ባለመረዳትና ትናንሽ ነገር ላይ በማትኮር፤ ሁለትም ጉራጌ የገጠመው የመሰልቀጥ አደጋ ሳይገባቸው ቀርቶ በሚፈለገው ቦታ ትግሉ ውስጥ የሉም። በብሔር ፖለቲካ ተጥዶና በትህነግ የፖለቲካ መስመር እየሄዱ የጉራጌንም ሆነ የሀገርን መብት ማስጠበቅ አንደማይቻል ሁሉ በሔርተኝነት ትግሉን ተጸይፎና ዳር ቆሞ በምኞት ብቻ ጉራጌን

የሚያድን እና ኢትዮጵያን የሚያዋልደው የፖለቲካ መስመርም አይመጣም። አሁንም ሁላችንም የጉራጌ ብሔርተኝነት ጥላ ስር ሆነን፤ ነገር ግን በዚህ መንገድ የሚገኝ ዘላቂ ፖለቲካዊም ሆነ መንፈሳዊ ስኬት እንደማይገኝ ተገንዝበን፤ የእስከዛሬ ቁጭታችንን መቋጨት አለብን። እንንቃ ትግሉ ጎሳን መሰረት ያደረገ ፖለቲካ የመደገፍ ጉዳይ ሳይሆን የአመክንዮአዊነትና የሰብአዊነት ነው። ያኔ ጉራጌ ህዝብ ያሉትን social & political capital ተጠቅሞ በአካባቢውና በሃገሪቱ ሰው ሰው በሚሸት ፖለቲካ የአስተዳደር (ሀገረ መንግስት) እንዲመሰረት የበኩላችንን አወንታዊ ሚና ለምንወግንላት ሀገራችን ልንጫወትና እንችላለን። ይህ በችሮታ የሚገኝ ሳይሆን በትግልና በመስዋትነት የሚረጋገጥ በመሆኑ ቆፍጠን ብሎ መቆም ያስፈልጋል።

## 5) ወቅታዊ የገራጌ ፖለቲካ ተዋናዮች ሁኔታ

ጉራጌ በ30 አመታት የኢትዮጵያ ፖለቲካ ማንነቱን ጨምሮ ሁለንተናዊ ቁሳዊና መንፈሳዊ ሀብቶች እንዳልነበር ሆኖ ወድመዋል። ተዘርፈዋል። ከስርአቱ ብልሽቶች የተነሳ የጉራጌው በነዚህ አመታት ማንነቱና አንድነቱ ከመቸውም ግዜ በላይ አደጋ ላይ ወድቆ ይገኛል። ይሄ እኩይ ቡድን ሀገሪቱን በመራባቸው ዘመናት የሀገሪቱን ነባር እሴቶች አውድሞ፣ ቅራኔዎችን አለቅጥ ለጥጦ በሁሉም የሀገሪቱ አካባቢዎች ተመሳሳይ ዉድመት እና ዝረፊያ ቢያደርስም በጉራጌው ላይ የደረሰዉ ዉድመት በአይነቱም ሆነ በይዘቱ ከሌሎች ይለያል። ጉዳዩን የከፋ የሚድርገው ነገር አኛ በዚህ ችግር ልክ ተደራጅተን እና ተግብባብተን በመቆም ይህን ሴራ የማክሸፍ አቅም ያልገነባን እና ህዝባችንም መከታ የሌለው የገዢዎችና የባለ ጊዜዎች መፈንጫ፣ እኛ ልሂቃኑ ወደን እና ፈቅደን ለህዝባችን የሚጠቅመውን የፖለቲካ አስተላለፍ እየተከተልን ሳይሆን ህዝቡ ፈርቶና ደህንነቱ ሰግቶ፤ በገዛ ሀገሩ መከታ አጥቶና ሁለተኛ ዜጋ ሆኖ ዛሬም እየኖረ መሆኑ ነው።

በዚህ ሳያበቃ በብልጽብና፣ በኢዜማ፤ ጉህን በመሳሰሉ የፖለቲካ አደረጃጀቶች እንዲሁም 30 በላይ በሆኑ በጉራጌው ህዝብ ስም በነጻ ማህበራት ተደራጅተው ያሉ ልዩ ልዩ የጉራጌ ህዝብ ጥያቄ አቀንቃኞች በጋራ ጥቅም መሰባሰብና መምከር ዙርያ ትልቅ ጉድለት አለባቸው። የህልውና አደጋውን የሚመጥን ዝግጅት ከማድረግ ይልቅ መተማመኛ እንዳለው ህዝብ ንድም መዘናጋት እንድም ተስፋ መቁረጥ ይታያል። ከዚህ አኳያ በትግላችን የቆመለትን አጀንዳ የተወሰነ ጊዜ ሊወስድ ቢችልም፤ ዘረኛውን ስርዐት ፈጣሪዉን ህወሀትን በማጥፋት እና የብሄር ፖለቲካን ተቋማዊና ሁልተናዊ ቅቡልነት ከማሳጣት ባሻገር በምትኩ ሁሉን አሳታፊ እና አካታች ተቋማት መገንባት አሑን ላይ ጉራጌውም ሆነ ሀገሪቱ የሚኖራት ብቸኛ አማራጭ መሆኑን ተቀብሎ ያለ አማራጭ መታገል ላይ ብዥታና የቆራጥነት መጓደል ይታያል።

ከለውጡ ዋዜማ ጀምሮ ዛሬ ድረስ አብዛኛው የጉራጌ አካባቢ ተወላጅ ፖለቲከኞች፣ ታዋቂሰዎች፣ ባለሃብቶች፣ ምሁራን እና የህብረተሰብ አንቂዎች ከዚህ በፊት በመካከላቸዉ የነበሯቸዉን ጥቃቅን ልዩነቶች አስወግደዉ ወይም አቻችለዉ ለሁለንተናዊ ለውጥ ጊዜያቸዉን፣ እዉቀታቸዉን፣ ጉልበታቸዉን እና ገንዘባቸዉን አስተባብረዉ የመሪነት ሚናቸዉን ለመወጣት የመወሰናቸዉ ጅምር አብዛኛዉን ህዝብ ያስደሰተ ቢሆንም ለማመን በሚስቸግር መልኩ ከብዙ አቅጣጫ አሉታዊ ፍላጎት ተወጥሮ ከጅምሩ እስካሁን ፈተና ውስጥ ወድቆ ይገኛል። እነዚህ አምስት ዋና ዋና አይነት ቡድኖችና አስተላለፎች ይለያሉ። እነዚህ አምስት ቡድኖች ይሄንን የጉራጌ ህዝብን ትግል አሉታዊ ተጽኖ አሳርፈውበት ይታያል። በዝርዝር እንመልከታቸው፡-

አንደኛዉ በታላቁ የጉራጌና የመሰለ የተገመደ ‹‹ታላቅ የወል ማንነት›› በመከፋፈል ኢትዮጵያን አንድነት በማፍረስ ህልም ውስጥ ሲሰራ የቆየው የህወሃት ቡድን ፖለቲካ ህልምና ውጤት ነው። ጉራጌነትን የማፍረስ ሴራ በማወቅም ሆነ ባለማወቅ ከራሱ ከኢሃዴግ ግምባር ጀምሮ ‹‹ስልጤ›› ፣ ‹‹ወለኔን›› ቤተ-ጉራጌዎችን ማንነት ማስከካድ የቻል፤ ከጉራጌ አብራክ የተገኙ ውህድ ማንነትን ያላቸውን ህዝቦች ለጠባብ ብሄርተኝነት የሰዋ፣ ነባር የህዝቡን እሤቶችና ግዛቶችና በርካታ የቤተ ጉራጌ ግዛቶችን ለኦነግ ማባበያ የሸጠ፤ እንደ ቀቤናና ማረቆ ያሉ ማህበረአቦች ጋር ልዩነት እያጦዘ እራሱን በጠባብና ትናነሽ ሁኔታዎች ውስጥ ወስኖና አሳንሶ ታላቁ የጉራጌ ማንነተ እየነጠለና እያወጣ የሄደ፤ የጉራጌውን ከሀገር ወዳድነት አውርዶ ለማሳነስ እና የሌሎች ብሄረሰቦች የስጋት ምንጯ አድርጎ በማቅረብ ጉራግዉ በጥርጣሬ እብዲታይና የጥቃት ሰለባ እንዲሆን የሚያደረግ ሐይል ነው። ይህ ሓይል ለተልኮው ህወሃትና መሰል አገር ጠልና አክራሪ ድርጅቶች አይዞህ ባይነት የሚመራ፣ በጥላቻ የታወረ፣ በእቅድና በፕሮግራም የሚሰራ፣ ጉራጌውን ከሃገራዊም ሆነ ከራሱ ህዝባዊ ጉዳይ እንዲገፋና ባይተዋር እንዲሆን የሰራ እና ያስካ ኃይል ነው። ዛሬም የዚህ ሃይል ወራሾች የጉራጌ ብሄርተኝነት እና መሰባሰብን እንደ ስጋት የሚያዩ፤ መደራጀታችን የሚያስደነግጣቸውና አይናቸው የሚቀላ፤ በተቻላቸው መጠን ህዝቡን የሚከፋፍሉ አጀንዳዎች በማቀባበል፣ የልዩነት አጀንዳዎችን በማራገብ ውዘተ ተግባራት እየተፈጸሙ ያሉ ናቸው።

ሁለተኛው በጉራጌ ህዝብ ዉሥጥ ሆኖ በህዝቡ ስም እየማለ ነገር ግን ለጠላት የሚሰራ ባንዳ እና ተላላኪ ቡድን ይሄንን እንደ አጋጣሚ በመዉሰድ በጉራጌ ፖለቲከኞች እና ልሂቃን መካከል ልዩነት ለመፍጠር ጉዳዩን ከሚገባዉ በላይ ያስጮኸዋል። ከለውጡ በፊት በህዝቡ ለአመታት ህወሀትን ከፋፋይ አገዛዝ ለመጣል በተለያ መልኩ በተደራጀና ባልተደራጀ መልኩ ሲያደርግ የቆየውን ረጅሙንና እልህ አስጨራሹን የጉራጌ ህዝብ ትግልና ሲፈጽመዉ የነበረዉን አኩሪ ገድል ሲያዳክምና ሲከፋፍል የኖረና ያለ፤ በለውጡ ዋዜማና በለውጡ ማግስት

‹ዘርማ› ላይ ሲፈጸም እንደነበረው ትግሉንና ድሉን ለማጠልሸት አልፎም አሁን አሁን ህዝባዊ ተጋድሎ ውጤት የሆነውን ድል ለመሻማት ላይ ታች ሲል የሚውለው፤ እንዲሁም ደግሞ ደግሞ የዉስጠ ፓርቲ የስልጣን ሽኩቻዉን በአሸናፊነት ለመወጣት ይሄንን ጉዳይ እንደ ካርድ በመጠቀም ተቀናቃኙን ከስልጣን ለማስወገድ የሚጠቀም ነው። ይህ ሃይል በትልቁ የህወሀት ህልም ተጋሪና የአጀንዳው አስፈፃሚ ሆኖ ጉራጌን የሚከፋፍል እና ለማዳከም የሚሰራ ስብስብ ነዉ። ዘውጌ ወለዱ ፖለቲካና የዘውጌ አስተዳደር እንዲቀየርና ጠንካራ ሀገረ-መንግስት እንዲኖር የማይፈልግ በጥቅመኛ ፖለቲከኞች የሚመራ በጉራጌ ስም የሚነግድ አንዳንዴም ላይ ላዩን ለህወሓት ጥላቻውን የሚገልፅ፣ ህወሓትን እየታገልኩ ነው የሚል ነገር ግን ውስጥ ውስጡን ህወሓት አጋሬ ነው የሚል በመንደር ፖለቲካ የሰከረ ቡድን ነው። የጎሣ ፌደራሊዝም የሚነካው በመቃብራችን ላይ ነው እያሉ በአደባባይ የሚቅራሩትን ትተን ከዚህ አጀንዳ ወጥን እንታገል ቀጥ ብለን ለህዝባችን በሚበጀው ‹‹የጥቅምና የሃሳብ ፖለቲካ›› ዙሪያ ህዝባችንን ይዘን እንቁም ስትለው በጠቅላላው "መንግስት" ተብዬው በኢትዮጵያ ውሥጥ የሃሳብ ፖለቲካ እንዲተከል፣ የጎሳ ፖለቲካ እንዲከሥም ቁርጠኛ ስለመሆኑን ዋስትና የሚጠይቅ፤ የውድቀት ፖለቲካን እየጋበዘ አማራጭ አልባና ሌሎች እድል ፈንታችንን ወስነው የሰጡንን ተቀብሎ ህዝባችንን ለባርነት የሚያመቻች ነው። እነኝህ የተለያዩ አይነት አስተላለፍ፣ ቡድናዊ ቅርፅ እና አደረጃጀት ቢኖራቸዉም በማወቅም ይሁን ባለማወቅ የጠላትን ተልእኮ ለማስፈጸም እና የጉራጌውን መከራ ለማራዘም መዳከራቸዉ ተመሳሳይ ያደርጋቸዋል።

ሶስተኛው ጎራ ደግሞ ፈራ ተባ እያሉ እንደገበያው እያወሩና እየሸጡ የሚኖሩ የሚታመኑለት ሆነ የሚሞግቱለት ሃሳብ የሌላቸው ወላዋዮች፤ ከየትም ወገን የምትሰጣቸውን አጀንዳና ወሬ እየሸጡ የሚኖሩ ሰነፍ ፖለቲከኛ፣ ምሁር፣ ነጋዴ፣ አክቲቪስት ወዘተ ተብዬ ስብስብ ነው:: ከነዚህ ከወላዋይ፣ ተለጠፊና የሃሳብ ደሃ ጋር አብሮ አምኖም ተማምኖ መታገልም ሆነ መምከር የሚፈልግ የሀይል አካል ስለማይኖር ዋናዎቹ የትግላችን አዳካሚዎችና ገዳዮች እነኚህ አድሃርያን ናቸው:: ሌላው ቢቀር ለሆዳቸው ሲሉ ብቻ እራሳቸውንና ህዝብ የሚጠቅሙ ሀሳቦች ሌሎች ታግለው እንዳይፈቱትና መልክ እንዳያሲዙ እንኳ የማያግዙና የማይወግኑ ለአጥፊ መሪዎችና ቡድኖች ሽፋን የሚመቹ፤ ስህተትን የማይቃወሙና የማያርሙ፣ ለሃሜት የተፈጠሩ፣ ያልሆነውንና የሆነውን በመቀባጠር ህዝብንን ከብሔርተኝነቱ የትግል አቅጣጫና ኢላማ የሚያስቱ፤ ለታይታ እና ለማሽቋለጥ በታዎናች የአጋጣሚ ተጠቃሚ (opportunist) ስብስቦች ናቸው:: ይሉንታ ቢስ በመሆናቸው ነገሮች ላይመለሱ አቅጣቸውን ቀይረው ወደ ገደል ሲያመሩ ተሸብለው ከጊዜና ሁኔታ ጋር እራሳቸውን

አስማምተው የሚኖሩ የትናንትም፣ የዛሬም የነገም የለውጥ ጠላቶች ናቸው:: አሁን በዚህ ሰዓት እንኳ የኃይል ሚዛን ወደ አጋደለበት ለመወደቅ እየጠበቁ ነዉ።

አራተኛው የሃይል ነባራዊ ሁኔታው የወለደው ሆኖ በህዝባዊ ትግል ውስጥ ዋጋ ያላቸው፤ ይብዛም ይነስም ህዝብን ማቀሳቀስና መምራት የቻሉ፤ ፖለቲካውን ነገር ግን በጥልቀት የማይለዩ፤ በግርግር በተኩላዎች እየተለጠፉና ነገሮችን በተንሸዋረረ መነጽር እየተመለከቱና የሴረኛ ፖለቲካና ፖለቲከኞች መሳርያ የሆኑ ቡድኖች ስብስብ ነው። እነዚ ውስጥ በጉራጌው አጀንዳ ተሸፍኖ ግዜያዊ ጥቅም አማልሎት የሚንገራገጨውም ሆነ በጠላቶቻች ሴራ ተጠልፎ አሻግሮ የጉራጌውን ስቃይ ባለመተንበይ እና ባለመመልከት የጎመራውን መሰባሰብባና ብሄርተኝነቱን ሰፊ ጥላ እና መሰባሰብያ አድርጎ ከመታገል ይልቅ ትናንሽ ቅሬታና ምሬቶችን ሰበብ እያረገ ትናንሽ ስብስቦች ስር በመበታተን የትም ፈቅ በማያረግ ሁኔታ የሚኳትኑበት ኃይል ስብስብ ነዉ። እዚህኛዉ ግሩፕ ውስጥ አብዛኛዉ ሰዉ ነገሩን ከግብሩና ከረጅሙ ጉዞ አኳያ ያልተመለከተው ሲሆን በግዜ፣ በአወንታ ተመልክተን እና በውግንና መንፈስ ከደረስንላቸውና ከታገዙ በቀሉሉ ወደ ትልቅ አቅም ሊቀየርና ሊጠቅም የሚችል ባብዛኛው የቀናዒ የወጣቶች ስብስብ በመሆኑ ብዙም መጨነቅ አያስፈልግም።

አምስተኛው የብዙሃኑ መገኛ ስብስብ ደግሞ እንደምንታዘበው በአንድ በኩል ባለ መልካም ምኞቶች፣ እንኳን ለጉራጌ ለሀገር የሚበቃ ፖለቲካ ካፒታል ያላቸው፣ ጉምቱዎች፣ ነገር ግን ለክብራቸው የሚጨነቁ በመሆናቸው ከችግሩ ጋር ተስማመምተው መኖር የመረጡ ናቸው። ነባሩ የፖለቲካ ብልግና ተጠይፈው የዳር ተመልካች መሆናቸው ግልጽ ነው። ነገር ግን ትግሉ በሚፈለገው ደረጃ እንዳይመራ እና ህዝቡ ቆርጦ እንዳይታገል እንቅፋት ሆነው ያሉበት የተበታተነ ሃይል ሲሆን ህዝቡን ከመከራም ሆነ ከአውሬ የማይታደጉት መሆናቸውን መረዳት ይጠይቀናል። በትግሉ ዙርያ መልካምና ሳቢ ሁኔታዎችን መፍጠርና የሚችል መሪ ቢኖር እነኚህን የአጀንዳው ተጋሪና የትግሉ ባለቤት በማድረግ ትልቅ ህዝባዊ አቅም ሆነው ለጉራጌውና ለሃገር የሚጠቀሙ ናቸው።

ከዚህ ዉጭ ያለው አስተላላፍ ዝም ብሎ በተለያዬ ምክንያት ለጉራጌ ይወግናል፣ እደግፈዋለሁ የሚለዉን ግለሰብ ወይም ቡድን ተከትሎ የሚነጉድ ነዉ። ይሄኛዉ ቡድን መጠየቅ፣ ማወቅ፣ መመርመር ለሚባሉ ነገሮች እምብዛም ነዉ። ግን ደግሞ የስድብ ሰራዊት ነዉ። የእኔ የሚለዉ ቡድን ወይን ሰዉ ከተነካ በቃ የሚወርደዉ የስድብና ፍረጃ ለምንቆምለት ህዝብና ትግላችን በተለይም ለክብሩንና ለምኞቱ መሰዋት ለሚከብደው ግን ደግሞ በትልቅ ደረጃ ማህበረሰቡን መጥቀም የሚችለውን ነፃ መሰባሰብና አቅም መሰናክል

ሆኖ እየጎዳን ያለ አካሄድ ነው። የጉራጌ ህዝብ ከደረሰበትን ቁሳዊ እና መንፈሳዊ ስብራት ለመታከም እንኳንስ የአብራኩ ክፋይ የሆኑትን የልጆቹን (ልሂቃኖቹን) አንድ መሆን ይቅርና የመላዉ ነባር የጉራጌ ህዝቦችንና ግዛቶችን ከዚያም አልፎ የመላዉ ኢትዮጵያን አንድነት አጥብቆ ይሻል። በመሆኑም ዛሬም ለዚህ የተቀደሰ አላማ መሳካት የጉራጌ አካባቢ ልሂቃን በአንድነት መሰባሰብና መንቃት ይገባል።

## 6) ለውጡ፤ ሀገራዊ የፖለቲካ ሁኔታዉ እና ብሄራዊ ምክክሩ

እንደ ሀገርም ሆነ እንደ ህዝብ ይህ የለዉጡ በጎ እድል ሊያመልጡን የማይገቡ ብዙ እድሎች ነበሩት። ነገር ግን እነዚ ተደጋጋሚ እድሎች የአሸጋጋሪነትን ሃላፊነት የወሰደው የዶክተር ዐብይ ፓርቲና መንግስት የህዝባዊ አመኔታዉን እና ድጋፉን በወጉ ሳይጠቀምና አደራዉን ሳይወጣ ቀርቶ አሁን መድረኩ በ‹‹ብሔራዊ ውይይት፣ ምክክርና እርቅ›› ለማሸጋገር የመጨረሻው ምእራፍ ላይ አድርሶታል። ይህ ምእራፍ የሃገራችን ልሂቃን ሀገራችንን ለማዳን የመጨረሻ እድላቸውን ነው ማለት ይቻላል።

ጉራጌዎች ለውጡን አንዳንዶች የሰጡን እንደሚስመስሉት ሳይሆን ከሌሎች ኢትዮጵያዉያን ወንድሞቻችን ጋር በመስዋትነት የመጣ እንጂ በችሮታ ያገኘነው አይደለም። የመላው ጉራጌ ህዝቡ የአመታት ያልተቋረጠ ወደር የለሽ ህዝባዊ ትግል፣ የቅርቡ የወጣቶች ዘርማ/አርዴ/... ጥላ ውስጥ ተሰባስበው ህዝባዊ ተጋድሎ፤ እንደ ግንቦት ሰባትና በመሳሰሉ የተለያዩ ሃገራዊ የፖለቲካ ድርጅት የተሰባሰቡና እስከ ትጥቅ ጥግል አማራጭ በወሰዱ፤ በህዝባዊ ማህበራትና ድርጀቶች ጣላ ስር የህዝብ ድምፅ ሆነው በኖሩ፤ ከህዝባችን አብራክ በወጡ እንኳን ብሔራቸውን መላዉ ኢትዮጵያን ድምፅ የሆኑ ሐገር ወዳድ የኪነጥበብ ባበሞያዎች፣ ባለሃብቶች፣ ምሁራን፣ አክቲቪስቶች፣ ጋዜጠኞች እንዲሁም ጥቂት በገዢው ፓርቲ ውስጥ የነበሩ አመራሮችና አባላት ህዝባዊ ትግሉ በፈጠረው በተፈጠረው የለውጥ መነቃቃት በዉስጠ ድርጅት ትግሉ በመሳተፍ፣ የከፈሉት መስዋትነት፣ ረጅምና ያልተገደበ እንቅስቃሴ አድርገዋል እያደረጉም ይገኛል።

በውስን ደረጃም ቢሆን ለውጡ እንደ ሰብአዊ መብት ኮምሽን፣ ብሄራዊ የእርቀ ሰላም ኮምሽን እና ምርጫ ቦርድን የመሳሰሉ ተቋማት ግንባታ፤ የነጻ የግል ሚድያ ተቋማትና በተነጻጻሪም ቢሆን ነጻነት ያላቸው ድርጅቶች መበራከት ካልሆን በቀር እልፍ አላልንም። ዛሬም ድረስ በበርካታ ሕዝባዊ ጥያቄዎች ይዞ የተነሳው ትግላችን፣ ህገ-መንግስታዊው ስርቱን ጠብቆ የቀረበው የጉራጌ የክክል ጥያቄው ምላሽ አልሰጠም፣ የልማት ጥያቄዎቻችን ሰሚ ማጣታቸው፤ እንደሃገር የመንግስት ሚድያዎች የህዝብ ድምፅ ከመሆን ይልቅ የፓርቲ ልሳን ሆነው መቀጠላቸው፤ የህዝባችን፣ ሞት ስደትና መፈናቀለቀል፣ ከዞኑ ውጭ ያሉ ጉራግዎች የሰቀቀን ኑሮ

መግፋታቸው መቀጠሉ፤ ስራ አጥነት፣ የኑሮ ውድነት የህዝባችን ስቃይ አርዝመዉታል። ይህም ሆኖ ህዝባችን በብልሃት ረድፍ ሳያዛንፍ በብዙ አይነት ነበባርና አዳዲስ ችግሮች ውስጥ ሆኖም በፅናት ከሃገሩ ጎን በመቆሞ ‹‹ከኔ ችግር የሀገሬ ይብሳል፤ ሃገር ሲኖር ሁሉም ይደርሳል›› በሚል ሆደሰፊነትና ታጋሽነት ሀገሩ ድረስልኝ ባለችዉ ሁሉ ሳይጎድል ከጦር ሜዳ ውጊያ እስከ ህዝባዊ ደጀንነት የዘለቀ ጀግንነት ከመንግስትና ከኢትዮጵያ ህዝብ ጋራ ሆኖ እየፈፀመ ይገኛል።

ለዉጡ አመታት ኢትዮጵያን ለማዳን የተሰነቀውን ያህል በጠላቶቻን እና በውስጥ ጥቅመኞች መዋቅራዊ ትስስር ፈጥረው ጥቅሞቻቸውን ካላስቀጠሉ ሃገር አልባ ሊደርጉን የተፈተንበት፤ ሁሉ አቅሞቻችንን በህዝባዊ ተሳትፎና ትግል በመመከት ድል የተቀዳጀንበት ግዜ ነው። መሳካቱ ጉዳይ እናዳለ ሆኖ ዛሬ ‹‹ሁሉ አቀፍና አሳታፊ ምክክር›› በኢትዮጵያ የፖለቲካ ችግሮች ላይ ማድረግ አማራጭ የሌለው መፍትሔ መጀመርያ መሆኑ ታምኖበታል ማለት ይቻላል። ምናልባት የቀረው ነገር ቢኖር ውጤታማ፣ ታማኒና ቅቡልነት ያለው እንዲሆን እነማን መሳተፍ አለባቸው እና እነማን ገለልተኝነታቸው ታምኖነት ምክክሩን ይምሩት …ወዘተ የሚሉ ነገሮች ብቻ ናቸው።

ወሳኙ ጥያቄ አሁን ይህ ትውልድ ያደሩና አዳዲስ ቅራኔዎችን በዕርቅና ይቅርታ ቋጭቶ፤ የጥንት ስልጣኔና ከፍታዉን የሚመጥን፤ በሃገራችን ውስጥ ሁሉንም ሃይማኖቶችን፣ ሁሉንም ማኅበረሰቦችን፣ እንዲሁም ሁሉንም ዜጎች በእኩልነትና በፍትሃዊነት የሚያስተናግድ ሥርአት ማቆም አማራጮችን ይዞ በመቅረብ በመደራደር እና በመወሰን አድስ የፖለቲካ ምዕራፍ ይከፍታል ወይ የሚለው ነው። ከኛ አኳያ ደግሞ ተደራቢው ቁልፍ ጥያቄ የአገም ጠቀም ፖለቲካችን አሁን በያዘው ቁመና በርግጥም ድምፃችን አልተደመጠም፣ አልተወከልንም፣ ህዝባችንን ያላሳተፈና ጥቅማችንን ያላስከበረ ነው ከምንለው ከ1983ቱ የአገራዊ ምክክርና የሽግግር መንግስት ምስረታ፤ እንዲሁም ከ1987ቱ ህገ-መንግስት የማፅደቅ ሂደት ከነበረው ነገር ምን ተምረናል የሚለውም ነው።

ሆነም ቀረ መንግስት ለጥያቄዎቻችን ከአንድ ወገን መልስ ሰጭነት ወደ የጋራ መፍትሔ አፈላላጊነት ከፍ ብሎ/ወርዶ ሁሉም ወገን በሀገር ልጅነትና በሰከነ መንፈስ እንድንመክርና ችግሮቻችንና በመጻኢ እድሎቻችን የመጨረሻውን ዉይይትና ውሳኔ እንድናደርግ አምኖ ተቀብሏል። ብሄራዊ ዝግጅት እያካሄደም ይገኛል። በነገራችን ላይ ይሄን ስል ብልፅግና እንደ ማንኛውም አንድ ተደራዳሪ አካል ለሃገር ይበጃል የሚለውን ሀሳብ

ይዞ የሚቀርብ እንጂ ብሔራዊ ምክክሩም ሆነ በብሔራዊ እርቁ የማስተባብርም ይሁን ድርድሩን የሚመራበት ወይም አቅጣጫ የሚሰጥበት ምንም አካሄድ ሊኖር አይገባም።

አሁን በሃገር ደረጃ የታሰበው ብሔራዊ ምክክርና ዉይይት ለህዝባችን በረከቶችን እንዲያመጣ በተስፋና በሃገራዊ በወንድማማችነት መንፈስ በመሳተፍ እንዲሁም ከፍሬው ለመብላት የሚጠበቅብንን ሃላፊነት መወጣት ያለብን ወቅት ላይ እንገኛለን። ብሄራዊ ምክክሩ አንድነት እና የብሄር ማንነትን አስማምቶና ነባሩን አንዱ አንዱን የመጨፍለቅ እና የአንዱ ህልዉና በአንዱ መክሰም ላይ አለመቆሙን የተረዳ፤ ሁለቱም አስፈላጊና ሊስማሙ የሚችሉ መሆናቸውን ከራሳችን ህዝብ ታሪክና ልምድ በማስተማር፤ ነባርና አዳዲስ የተቃርኖዎቻችንን ምዕራፎች ሁሉ በይቅርታና በዕርቅ የሚቋጭና ወደፊት የሚጓዝ የማድረግ ሃላፊነት አለብን።

## 7) ወቅታዊ የጉራጌ ህዝብ የትግል አቅጣናጫ እና ብሄራዊ ምክክሩ

የመጀመርያው ጉዳይ የጉራጌ ጉዳይ ‹‹ከፓርቲ ፖልቲካ›› በላይ መሆኑን መግባባት ነው። ልዩነትና አቻችሎ ሁሉንም ወገን መሰባሰብ ነው፡ ብቸኛው መውጫው መንገዱ ደግሞ ገቢራዊ መፍትሔ መንገድ መከተል ነው። መሬት ላይ ያለው እውነታ ተረድቶ፣ ምን ማደረግ አለብን ብሎ መጀመር ነው። Pragmatic በመሆን አሁን መሆን ያለበትን ማድረግ ነው ብልሃቱ። እኛም በሚጀመረው ምክክር (ድርድር) ላይ ምን እንደሚገባን፤ ምን እንደምንጠይቅ፤ እነማንን እንደምናሳትፍ፤ እንዴት ባለ አስተላለፍ ተጉዘን እንደምናሳካው ማሰላሰልና መምከር አለብን። ጀርመናዊው ኦቶ ቮን ቢስማርክ ‹‹ፖለቲካ የሚቻለውን፣ የሚደረስበትን፣ በቅርብህ ያለውን፣ የተሻለውን የምታሳካበት ጥበብ ነው›› ይላል:: ‹‹የሚቻለውን/ the possible›› የሚለውን ቃል እንውሰድ። ‹‹አቅም›› ደግሞ አስቻይ factor እንደሆነ እናስታውስ፣ ‹‹አቅም›› ብዙ ነገሮች እንዲቻሉ (possible) እንደሚያደርግ እንረዳ። የቢስማርክን ብየናን ከፍ ስናደርገው ፖለቲካ የምንፎክርበትና የምናሽላላበት ጡሩንባ ሳይሆን ተጨባጭ ውጤት የምናስመዘግብበት ጥበብ እንደሆነ ይነግረናል። ፖለቲከኛ ነን ካልን deliver ማድረግ ይጠበቅብናል፣ ፖለቲካ መልካም ምኞታችንን የምንገልፅበት መድረክም አይደለምና።

በመድረኩ ወዳጅ እና ጠላት ማን እንደሆነ መለየት ብቻ ሳይሆን የወዳጅነቱን እና የጠላትነቱን ልክ ማወቅ ያስፈልጋል። በፖለቲካ ወዳጅ ማብዛትና ጠላት መቀነስ ወሳኝ ተግባር ነው። በፖለቲካ ወዳጅ ሲባል ወጥነት ያለው የአላማ ተጋሪ ብቻ አይደለም። ወዳጅ ማለት የሚታገልለት አላማ ብያኔውን ከሚሰጠው የፖለቲካ

ኃይል አላማ ጋር ፍጹም ተጻራሪ ያልሆነውን ሁሉ ያጠቃልላል። ከወዳጅ ኃይሎች መካከል የተወሰነው አጋር፣ ተገዳዳሪ፣ አቻ፣ ተቃዋሚ፣ ተፎካካሪ ወዘተ ይሆናል። ከወዳጅ ኃይሎች መካከል ተገዳዳሪ ወይም ተቃዋሚ የሆኑትን በምክር አሳምኖ የአላማ ተጋሪ ማድረግ ባይቻል እንኳ ጠላትነትን ቀንሶ በሚያግባቡ ነገሮች ላይ በጋራ መስራት መቻል የፖለቲካ ብቃት መገለጫ ነው። በፖለቲካ ዘላቂ ጠላት የለም የሚባለው ፖለቲካ የምክር ጥበብ ስለሆነ ጠላትን በሀሳብ በልጦ አላማውን የማስቀየር እድል ስላለነው። የጉራጌ ህዝብ ትግል የተሻለ ሀሳብ ያላቸው ቅን እና አስተዋዮች ያሉበት ስብስብ ስለነበረ ለዘውግ ፖለቲከኞችም ሆነ ለአንድነት ፖለቲከኞች፤ ለአማራም ሆነ ኦሮሞ፤ ሙስሊምም ሆነ ክርስትያን የፖለቲካ ኃይሎች ወዳጅ ነው ማለት ይቻላል።

የትኛውም የፖለቲካ ቡድን አላማውን በስኬታማነት የሚፈፅመው ቡድኑ በቆመለት አላማ ዙሪያ ፍላጎት ያላቸውን ሌሎች ኃይሎች ተደራድሮ/ተከራክሮ በመተማን የአላማው ተጋሪ ወይም አጋር ማድረግ ሲችል ነው። ለኛ መቅደም ያለበት አጀንዳ የብሔርተኝነታችንና ህዝባዊ ትግሉን በቅጡ ተሰባስበንና መክረን በገጠመን አደጋ ልክ ከወቅቱና ከጊዜው ጋር እራሳችንን መቃኘት ነው። በውስጣችን ያሉ ችግሮችንና ጠያቂዎችን እውቅና መስጠትና መቀራረብ አስፈላጊ ነው። ይህን ለውስጥ አንድነታችንን እና መተማመናችን መሰረት ነው። አንድነት በፍላጎት ወይም በለቅሶ አይመጣም፤ ማንነታችን እና አንድነታችን የሚያስጨንቀን ሰዎች አንድነት፤ በመተባበር፣ በመከባበር፣ በመተሳሰብ ወዘተ እንጂ በወሬ እንደማይመጣ ማወቅ አለብን።

አሁን ድርጅትን፣ ርዩተ-አለምን፣ ቂምን፣ ጎጥን፣ ፀብን፣ ኢጎን፣ ኩርፊያን… መሻገር እና በአንድ ላይ መቆም ይገባል። ባለው አደጋ ዙሪያ መሰባሰብ የግድ ነው፣ ሁሉንም ባለድርሻ አካላት የሚሳተፉበት ኮንፈረንስ ማድረግና በአደጋው ዙሪያ በጥልቀት መምከር ቅድሚያ ሊሰጠው ይገባል፣ እንዳስፈላጊነቱ አዲስ አደረጃጀት መፍጠር፤ ሁነኛ መሪዎችን መለየት የምክክርና ድርድር አጀንዳዎችን ማዘጋጀት፤ ነባራዊ ሁኔታዋችን በጥልቀት መተንተን፣ አቅጣጫ ማስቀመጥ፣ ወጥ እና እንደአስፈላጊነቱም ተለዋዋጭ ስትራቴጂና ታክቲክ መንደፍና ማስፈፀም ቀጣዩ ተግባር መሆን አለበት። መሬት ላይ ያለው ሀቅ ደግሞ ህዝቡን በሚያሰባስበው አጀንዳ ዙርያ እንድናሰባስበው እንድናነቃው እንዲሞግት የሚያስገድድ ነው።

ኢትዮጵያውያን ሁላችን የአንዳችን እጣፈንታ በአንዳችን ላይ የተመሰረተ መሆኑን አምነን ለራሳችን ችግሮች እራሳችን መፍትሄ መሻት ይጠይቀናል። ለጉዳዮቻችን በመመካከር ተቀራራቢ እና ሁላችንንም አሸናፊ የሚያደርግ መልስ መፍትሔ ማፈላለግ አለብን። የኛ የጉራጌ ብሔርተኞች ትግልም በውስጣችን እና በዙርያችን ካሉ የትኞቹም አመለካከቶችና ፍላጎቶች፤ ቡድኖችና ግለሰቦች ጋር የጋራና የተናጠል ችገሮቻችን የትኞቹም

ጥያቄዎች መፍትሄ ለማበጀት ከዚህ የተሻለ ምንም አይነት አማራጭ የለንም። እርስ በእርስ የተጠፋፋንዉና የተበዳበለውን በፍትሃዊነት ተወቃቅሰን መፃኢዉን ዘመን የእኛ ማድረግ እድል እጃችን ላይ ወድቋል።

በትግላችን የተገኘው የለውጥ በፈተና ውስጥም ሆነው ለእውነተኛ ዲሞክራሲ መንገድ የሚቀየሰበት፤ ነጻነት የምንቀዳጅበትን፤ በፖለቲካ መድረኩ ሁላችንም የትኛውንም አይነት ሃሳቦች መደመጥ የምንጀመርበት የማይስማሙንን ሀሰቦች የማድመጥ እና የማክበር ባህላችን ማሻሻል ተስኖን ፀብያለሽ በዳቦዎች ሆነን ከቆምንበት አሁንም የመለወጥ ዕድል (ፀጋ) ያስገኘልናል። ከወዲሁ መክረን በብልሃት የምንገነባው ይህ እሴት የመደመጥና ተቀባይነት ሁኔታችንን ያሻሽልልናል። እንዲሁም የዘመናት ህዝብ የሚያነሳቸው የፖለቲካ ጥያቂዎች ምላሽ ማግኘት ቁልፉን ከመቀዳጀት አልፎ በሴረኞች ሃገር ጠል ልሂቃኖች ዘንድ ‹‹በሀገር ወዳድነታችን›› ምንያት ከኮሰስንበት እና ከተገፋንበት ብሄራዊ የፖለቲካ መድረክ እንድንመለስ ያስችለናል።

ወደ ብሄራዊ አጀንዳችን ስንመለስ የሀገሪቱ ልሂቃን ለጊዜው ከውጭ የተኮረጀ እንጂ ሀገር በቀል ነባር ስልጣኔዎችን ላይ የተመሰረተ ማህበረሰባችንን የሚመጥን የፖልቲካ ፍልስና ይዘው አያዉቁም። እንደ ጉራጌና ወሎ ላለ ለተሰናሰለ እና ለተፈተለ ማንነት ላለው ማህበረሰብ ፈዉስ ከመሆን ይልቅ ለጠርዘኛ ፖለቲካ እሳቤዎች ልባቸው ያደላል። ለዚህም ነው ለሀገርም ሆነ ለራሳችን የውሰጥ ችግሮች ለመፍትሔ ወደ ውስጣችን በመመልከት ከነባር የጉራጌ ላእላይ ዕሳቤዎችና እሴቶች በመነሳት እንቅረብ የምለው። ይህን መራራቅ ለማቀራረብ መፍትሄ ለመሻትም ነው ሀገሪቱ ብሔራዊ ምክክርና መግባባት መድረክ መጥራቷ። እኛም እራሳችንን የሚመስል፤ ለሀገሪቱም ፍቱን የሆነ መፍትሔ ይዘን አንድም እራሳችንን ሁለትም አገራችንን ማዳን እንችላለና። እንደገና ማሰብ እንጀምር።

አሁን ያልተነካው መንገድ የእውነተኞቹ ጉራጌዎች የባህሪይ መገለጫ ብቻ የሆነው ብልህነት ከሁሉ ያስበለጠው የቅንነትና የስክነት መንገድ ነው። ይህ እንዲሳካ በቀጣ በሚደረገው ሀገራዊ የምክክር መድረክ "ታሪክ" ዋነኛ አጀንዳ እንዳይሆን ሚዛን ማስጠበቅ ሚና መጫወት አለብን። ታሪክ ዋነኛው የሀገራዊ መግባባት እና የፖለቲካ አጀንዳ ከሆነ መድረኩ እንደ ተለመደው መነታረኪያ ሆኖ የታለመለትን ውጤት ሳያመጣ ይቀራል። እኛም እንደ ሐገር ባለቤት ዋነኛ ጉዳያችን መሆን ያለበት ሀገራችን ያሉባትን ዘርፈ ብዙ ኢኮኖሚዊ፣ ፖለቲካዊ እና ማህበራዊ ችግሮች ለይቶ ችግሮቹ በአጠረ ጊዜ ተቀርፈው ለሁላችንም የምትሆን አንዲት ጠንካራ ሀገር እንዴት እንገንባ? የሚለው ነው። እዚህ ሀሳብ ውስጥ የእኛም የሌሎችም ጥያቄዎች መልስ ይገኛል።

**1ኛ)** ዋነኛው አጀንዳ መሆን ያለበት ጉዳይ "በተቻለ መጠን ለሁላችንም እኩል የምትመች ጠንካራ ሀገር መገንባት" አለብን የሚለው በመሆኑ ሁሉም አካላት እኩል ታምኖበት ነው ምክክሩ መጀመር ያለበት። ዋነኛው ጥያቄችን ከድህነት የተላቀቀች ጠንካራ ሀገር እንዴት እንገንባ የሚል ሆኖ እያለ ባለፈ ታሪክ እየተነታረክን መቀጠል የለብንም። በታሪክ ላይ የተቸነከረ ፖለቲካ ልዩነት እና ጾብን አንግሶ እርስበርስ ስንሻኮት ህዝባችን (የሁሉም ብሄሮች ድሃ) በመከራ ውስጥ እንዲቀጥል ከማድረግ የዘለለ ውጤት እንደማያስገኝ ላለፉት ሰላሳ አመታት ሞክረን ጥቅም እናጉዳቱን አይተነዋል።

**2ኛ)** ሌላው አበይት አጀንዳ "የብሄሮች መብት ሳይሸራረፍ መከበር አለበት" የሚለው ሲሆን ይሄም ከምክክሩ በፊት ሁሉም እኩል ተስማምቶበት መጀመር አለበት። የብሄሮች መብት ይከበር ሲባል የተነፈገው መብታቸው የሚሆነው ፖለቲካዊ፣ ኢኮኖሚ ወይም ማህበራዊ ጉዳዮችን የተመለከተነው የሚሆነው። ስለዚህ ይሄ የቡድን መብት የግለሰብን መብት ሳይደፈጥጥ በአግባቡ ተፈትሾ መልስ ሊሰጠው ይገባል። ህወሓት እንዳደረገው የሰማንያው+ ብሄሮች ጥያቄ አንድ እና ተመሳሳይ አስመስሎ ለችግሮቹ ሁሉ አንድን ብሄር እየወቀሰ ለየትኛውም ብሄር ጥያቄ (በልኩ መዝኖ) ተገቢውን መልስ የማያስገኝ ውሃ ቅዳ ውሃ መልስ አይነት የዜሮ ድምር ፖለቲካ መሆን የለበትም።

**3ኛ)** በዚህ ረገድ በሚደረጉ ምክክሮች ገና ከጅምሩ መግባባት ይደረግባቸው ያልናቸው "ጠንካራ እና የበለጸገች ኢትዮጵያ መፍጠር" የሚለው "የብሄሮች መብት ሳይሸራረፍ መከበር አለበት" ከሚለው ጋር መሳ ለመሳ ምላሽ እያገኙ እንዲሄዱ የሚያስችል መፍትሔ ታሳቢ ተደርጎ መሆን አለበት። ብሄሮች አሉን የሚሏቸውን ጥያቄዎች በራሳቸው ማቅረብ የሚችሉት ራሳቸው አምጥተው ጥያቄዎቻቸውን ለማቅረብ አቅም የሚያንሳቸውን መንግሥት አቅርቦ ፖለቲካው ሲስተካከል ለዚህኛው ብሄር ይሄን ይሄን ጥያቄ፤ ኢኮኖሚው ሲያድግ የትኛው ጥያቄ፤ ማህበራዊ ፍትህ ሲሰፍን ደግሞ የትኛው ቀሪ ጥያቄ በምን ያክል የጊዜ ገደብ ውስጥ መልስ ያገኛል የሚሉትን ተጨባጭ መፍትሔዎችን ለማመንጨት መሆን አለበት።

በነዚህ ነጥቦች ላይ እኛ የጠራ አቋም ይዘን ጠንካራ ሀገር እየገነባን፣ ችግሮቻችንን እየፈታን፣ እስካሁን ያልተመለሱ የብሄር ጥያቄዎች ካሉ ከየብሄረሰቦቹ ተጨባጭ ችግሮች አንጻር በግልጽ እየተለዩ መልስ ማግኘት ያለበትን እየመለስን መቀጠል እንጂ በብሄር ጥያቄ ስም ጥቂት አፈጮሌዎች ጾብ እና ጥላቻን እየሰበኩ ባልወከላቸው ምስኪን ህዝብ ስም ዘላለም እየነገዱ የሚቀጥሉበት አይሆንም።

## 8) አዲሱ ኢትዮጵያዊነት ከጉራጌነት ይወለድ

ለዘመናት ለኢትዮጵያችን ያበረከትናቸውን እሴቶች ለድኩማኑ የሀገራችን ኋላ ቀር የፖለቲካ ባህል ፈውስ እንደሚሆኑ ልንረዳ ይገባል። ጉራጌ ስልጡን ነው። ስልጡን ማለት ግዜውን፣ ቦታውን፣ ራሱን የዋጀ ማለት ነው። ጉራጌነት የሰሜኑ ባህል፤ ከደቡቡ ጋር ተዋህዶ የተፈጠረ ነው። በነባሩ እምነት፣ በእስላምና ከክርስቲያን የተቀመመ ነው። ለመስጂድም ለቤተክርስትያንም የታመን ማህበረሰብ። እያልን ያለነው ማህበረሰቡ ሰው የገነባበት ፀዴ እሴት አለው ነው። ለዚህ ነው አዲሱ ኢትዮጵያዊነት ጥንስሱ እዚህ ይሁን የምንለው። እርሾው ለዘመናት ተጠብቆ እና ደርጅቶ ጉራጌው መሐል ይገኛል። ትናንትን መርምሮ፣ ዛሬን አይቶ እና የነገን ገምቶ ከተፈጥሮ እና ከፍጡራን ሁሉም ጋር ተስማምቶ የመኖር ነባር ጥበብ ጉራጌው ጋር አለ።

ጉራጌ ለሀሳብ ልዩነት በጩቤ፣ በቦንብ፣ በአረር ለመተላለቀ ባህል ቦታ የለውም። ይልቅ ለድርድር፣ ለሰጥቶ መቀበል፣ ለውይይት የተመቸ ነው። ፀብና ጉልበተኛነት ይንቃል። በባህሉ አጥቂነትን፣ ግጭትን፣ ፀብን አያበረታታም። ለመግባባትና ለእርቅ ሁሉን ይሰጣል። ህዝቡ ሃሳብ፣ ፍላጎት፣ ውሳኔ ከግዜና ከሁኔታ እንዲሁም ከጠቀሜታው አኳያ ተመዝኖ እንደሚቀየር ያምናል። ማህበረሰቡ በትውልዱ ውስጥ ህይወት፣ ተስፋ፣ ህልም አጽንቶ አቆይቷል። ጉራጌ ማስተዋል፣ ጥበብ፣ እርጋታ ታድሏል። 'ምን ጎደለ? ምን ይጨመር? ምን ይቀነስ?' ብሎ ባለው ጨምሮ ሐገር እንዲኖረን ያስችለናል። ይህ ኢትዮጵያዊነት የጎደለው ቀለም ነውና ከጉራጌ ይሙላ። እቺን ሃገር ባለ ንዋይ ያደረገው ይህ እሳቤ ለፖለቲካችን መድረክም መዳኒት ነው።

ይህን ይዘን አዲሱ ኢትዮጵያዊነት ከጉራጌነት ይወለድ የምንልበት በተጨማሪ ነገሮችን እናንሳ። ጠንካራ የስራ ባናህል እና የመተባበር ዘመን ጠገብ እሴት ያለውና ይህንን እሴት መቅዳት የሚቻልበት ማህበረሰብ ነው። ጉራጌ ጉንዳን ነው። ስራ አይንቅና ሳይመርጥ ይሰራል፤ይሮጣል። ሌብነት፣ ምቀኝነት፣ ነገር፣ ሐሜት፣ ክፋት የለችበትም። የበሰበሰች ስሙኒ ወደ ሊስትሮ፤ ከሊስትሮ ወደ ጆብሎ ንግድ፤ ከዛም ወደ ባለአምስት ኮከብ ሆቴል ሲቀየር፣ እየተመለከተ ተአምራዊ ለሚሆንበት ሀገራዊ እሴትና ደካማ የስራ ባህል ባህር ማዶ ተሞክሮ ፍለጋ ለሚኳትነው ፖለቲከኛና ልሂቅ ይህንን ህብረተሰባዊ እሴት የተገነባበት ምስጢር ከመሰረቱ አጥንቶ ለሃገራዊ እድገት ምሰሶ ማድረግ ይቻላል ።

ቁጠባ እና ሀብት የመፍጠር ነባር እሴት ለኢትዮጵያ አሁንም እንናፈቃት ነው። አባካኝነትን ከለጋስነት፤ ቆጣቢነትን ከስስታምነት ጋር እምታቶ የሚተርክ ህብረተሰባዊና መንግስታዊ ባህሪ የሚያሰቃያት ኢትዮጵያ እፎይታዋ እዚህ አለ። መስራትና ገንዘብ ማግኘት ብቻውን ሀብት አያቀዳጅም የሚለው ጥንታዊ እውቀት ‹‹ቆጣቢነትን››፤ የተቆጠበችዋ ፍራንክ ፈጥና ወደ ስራና ተጨማሪ ኢንቨስትመንት ላይ እድትውል ደግሞ መተባበርና ተያይዞ የመበልጸግ ተምሌት የሆነችውን ‹‹እቁብን›› የመሰለ አይተኬ ህዝባዊ ተቋም ያበረከተ

ዛሬም ኢትዮጵያን አስተኛና መካከለኛ ቢዝነስን ተሸክሞ ማቆየትና የብዙሃኑ ከብሄረሰቡ የተገኙ ነጋዴዎችና ባለሀብቶች ሐብት መፍለቂያ መሰረት ነው። የሚገርመው ዛሬም ዘመናዊው አለም ፋይናንስ ተቋማት እንኳ ይህን ህዝባዊ እሴት የሚስተካከል ፈጠራና ስልጣኔ የላቸውም። የተኮረጀ ሲስተም ላይ የተመሰረተው የባንክ ስርአታችን እቁብን የሚስተዳድር አገልግሎት መጀመር በማስቻል ሀብት ከማፍራት ባሻገርም እርስ በርስ የመተጋገዝ ሃገራዊ እሴታችንን ‹‹ተያይዞ ሀብት የመፍጠርና የማደግ›› የኢኮኖሚ እሴትን ማሳደግ ይቻላል።

ሌላው ቤተሰባዊ መስተጋብር እና ስርዓት ስንዳስስ ጥልቅ ሀብት ጉራጌው ቀዬ እናገኛለን። ጉራጌ ቤተሰቡን ያፈቅራል። ለአባቱ፣ ለእናቱ፤ ለወንድም ለእህቶቹ ባሪያ ነው። በባዶ እግሩ ሄዶ፣ ታናናሾቹን ያሻግራል። ቀን ያወጣል። ፖለቲካ፣ ሴት፤ ገንዘብ አያታልለውም። ለህልሙ ባርያ ነው። ቀን ሲወጣለት ትናንቱን አይረሳም። መላው የኢትዮጵያ ህዝብ ለዚህ ምስክር ነው። ለመስቀል፣ ለአረፋ፣ ለኢድ ሃገር ቤት የሚገባውን መኪና እና የህዝብ ጎርፍ እየው። ከአሮጌ ፍራሽ፥ እስከ ዲሽ ታያለህ። ሌላዊ እሴት ስርዓት ነው። አንድ ማህበረሰብ ስርዓት ካለው ስልጡን ነው። ለስርዓቱ ማህበረሰቡ ለዚህ ስርት ተገዢ በመሆኑ እሴቱ አድርጓቸው ቆይቷል። ለእሴቶቹ ይታመናል። ስልጣንና ሃብት የሚባሉ የስዉሊጂነ ሰብና በእጅጉ የሚፈትኑ ነገሮች አሳስተው ሰውን በማናለብኝነት እንዳይበደል፣ ፍትህ እንዳይዛባ በርቼ/ጡር... ያስከመጠ ነው። ጉራጌ ለባህሉ፣ ለሃይማኖቱ፣ ለቤተሰቡ ታዛዥ ነው። ሽማግሌ ይፈራል፤ ያከብራል። ለሽማግሌ እርግማን ሲል የሰረቃትን ምላጭ ይመልሳል። ጠንካራ ስርዓት አለው። የልቦና ውቅሩ የተስተካከለ ነው ማህበረሰብ ነው። ይህንን እሴት ይዘን ነው አዲሱ ኢትዮጵያዊነት ከጉራጌነት ይወለድ የምንለው።

የእኛ ሀገር የዘመናት ፖለቲካ መላቅጡ የጠፋ፤ ጠላት እየፈለፈ የሚያድር እና ሄዶ ከመላተም የተሻለ ዘመን ተሻጋሪ አገር በቀል መፍትሔ ሆኖ ከገባንበት የፖለቲካ አጣብቂኝ ለመውጣት እንዲህ ያለ መዳኛ ያስፈልገዋል። በመነጋገር እና በመረዳዳት ለሁሉም የምትመች ነፃነት፣ እኩልነት፣ ፍትህ፣ የህግ የበላይነት እና ዴሞክራሲ የሰፈነባት፣ ዜጎች በማንነታቸው የተነሳ የማይጠቁባት እና አድልዎ የማይፈፀምባቸው፣ በየትኛውም ቦታ ያለስጋት ተንቀሳቅሰው የሚሰሩባት እና የሚኖሩባትን ኢትዮጵያ እውን ማድረግ እንችላለን ብሎ ማመን ያስፈልገል።

(**ማስታወሻ፡-** እንባቢ ሆይ ለዝች ንዑስ ርእስ ምልከታም ሆነ የፅሁፉ መነሻ ይኟንስ ደጉ የተባለ ሰው በፌስ ቡክ ገጹ ያጋራት መጣጥፍ ናት።)

## 9) መደምደሚያ

ምክክሩ በረከት አለው አሻራችንን ስናሳርፍበት የበለጠ ይሆናል። ረፍዷል። ግን ፈጥነን ከመድረስ ውጭ አማራጭ የለንም። ለማጠቃለያ እንዲሆኑ ለስኬቱ ቀጣይ መፈጸም ያሉብን ተግባራት ፍሬ ነገሮች ትኩረት መስጠት ያለብን እነዚህ ናቸው፡- አንደኛ የጉራጌን ልሂቃል ጋር በአጀንዳዎች መለየት፣ መግባባትና ወጥ አቋም መያዝ።

1) የሁሉም ችግራችን ምንጭ የሆነውን ህገ-መንግሰት ማሻሻል

2) የክልል አስተዳደር (ራስን በራስ ማሰተዳደር) ጉዳይ

3) ከዞኑ ውጭ ያሉ ጉራጌዎች መብት መከበርና ህጋዊ ውክልና ጉዳይ

4) ፍትሀዊ የልማት ተጠቃሚነት የሚጋግጥ አሰራር (የህግ ማዕቀፍ) ማኖር ጉዳይ

5) በዉስጥ ያሉ የህዝቦች የአደረጃጀትና የአስተዳደር ጥያቄዎች፣ አፈታት በህዝቡ የእርስ በእርስ ግንኙነት ማስተክከል… የሚሉት ዋነኛዎች ናቸው።

ሁለተኛ በጉዳዩ ላይ ግንዛቤ መፍጠር እና ህዝቡን ማንቃት ስራ መስራት ነው (ከሁሉም ባለድርሻ ጋር)። ሶስተኛ የሌሎችን ህዝቦችን ጥያቄዎች በውሉ መረዳት (በውስጣችን እና በውጭ)። አራተኛ አግላይ እና የጩኸት ፖለቲካ ማሰወገድ ስራ ነው። አምስተኛ እውነተኛ መሪዎችን መለየት ትግሉ ውስጥ ማሳተፍ እና በሂደቱ መሪ ሆነው እንዲወለዱ ማድረግ ነው። ይህም አንድም ለምክክሩ ብቃት ያላቸው፣ እምነት የሚጣልባቸው ተሳታፊዎችን መለየት ያስችላል። ሁለትም ለዘለቄታው በተደጋጋሚ የተደረጉ የህዝብ ንቅናቄዎች በኋላ የተበታተኑትን መሪዎች በማሰባሰብ፣ ነባሮቹን ወጣቶቹ በማስተሳሰርና በመማመርና በመደጋገፍ አዲስ ምእራፍ ለመክፈት ያስችለናል።

እንደርሳል!!

## 6) ዋቢ መፃህፍት


1) እነ ድምበሩ ዓለሙ፤ ጎጎት፤ የጉራጌ ብሔረሰብ ታሪክ ባህልና ቋንቋ አጭር ታሪክ፤ (1987 ዓ/ም)፤ አዲስ አበባ።

2) ጉህዲግ (የጉራጌ ሕዝብ ዲሞክራሲያዊ ግንባር) የፖለቲካ ፕሮግራም፤ (ሰኔ 1983 ዓ/ም)፤ አዲስ አበባ።

**3)** ሰይፈ ድባቤ፤ አዝማች፤ የጉራጌ ህዝብ አጭር ታሪክ፤ (1966 ዓ/ም) አዲስ አበባ፡፡

**4)** ገ/እየሱስ ኃ/ማርየም፤ ‹ህብረት ስራ›፤ (1970)

**5)** ናጋቱ ወልዴ፤ ትውፊታዊው የጉራጌ የመስቀል አከባበር፤ (2010)

**6)** አፈንዲ ሙንተኪ፤ የኤርትራ ህልም፤ (2008)

**7)** ታምራየው ሲማ፤ የጉራጌ ህዝብ ማንነት በኢትዮጵያ አንድነትና ነጻነት (ዕቅፍ ውስጥ) ፤ (2014 ዓ/ም) አዲስ አበባ፡፡

**8)** Emrates Professor Beharu Zewude, Society, State & History; Selected Essays, 2008, Addis Abeba Univeristy Press.

**9)** Professor Merera Gudinna, Ethiopia; Compiting Ethnic Natinalisms and the Quest for Democracy, 1960 – 2000. (2003) N.P Shaker Publishing.

**10)** Bew John, Realpolitic: A History. (2014) Washington D.C; The Library of Congrass

**11)** National Dailogue Hand Book, A Guide for Practitioner, (May, 2017) Berghof Foundation Operations GmbH.

**12)** የኢትዮጵያ አገራዊ ምክክር ኮምሽን ማቋቋሚያ አዋጅ አጭር ማብራርያ (2014ዓ/ም)